# ምዕራፍ ፫

## ትምህርት የሥልጣኔ መሠረት

ማንም ሰው እንደሚያውቀው፣ ሐምሌ 16 ቀን 1884 ዓ.ም ከራስ መኰንን ወልደሚካኤልና ከወይዘሮ የሺእመቤት ዓሊ ሐረርጌ የተወለዱት " ተፈሪ መኰንን" ከመስከረም 1909 ዓ.ም እስከ መስከረም 1967 ዓ.ም ድረስ፤ ለአሥራ አራት ዓመት በአልጋወራሽነት፤ ለአርባ አራት ዓመት በንጉሠ ነገሥትነት፤ በድምሩ ለአምሳ ስምንት ዓመታት መላ ኢትዮጵያን መርተዋል።

እንግዲህ ፤ በእነዚህ ረዥም ዘመናት ውስጥ፤ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መሪነት ኢትዮጵያ ከጨለማ ወደ ብርሃን ተሸግራ ከፍተኛ ዕድገትና መሻሻል አግኝታለች ብለው የሚያምኑት ወገኖችና፤ በተቃራኒው ደግሞ በእሳቸው አስተዳደር የተሠራው ሁሉ በቂ አይደለም በማለት ወቃሽ የሆኑት ተቃዋሚዎች፤ በአንድ መድረክ ላይ ተገናኝተው ቢወያዩ፤ ያለጥርጥር ሊያስማማቸው ከሚችሉት ነገሮች መጀመሪያ የሚሆነው ይህ በዚህ ምዕራፍ የሚቀርበው የትምህርት ጉዳይ ነው ብለን እናምናለን። ይህንንም ማመን የምንችለው ዘመናዊው ትምህርት በኢትዮጵያ የተስፋፋው ከምን ደረጃ ተነሥቶ ለብዙ ዓመታት ምን ያህል ጥረት እንደተደረገ፤ ትክክለኛውን ታሪክ ቅንና እውነተኛ በሆነ መንፈስ የተመለከትን እንደሆነ ነው።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የኢትዮጵያን ዕድል በመሪነት ከያዙበት ጊዜ ጀምሮ፤ ዘመናዊ ትምህርትን ለማስፋፋትና የኢትዮጵያ ልጆች ተምረው፤ ለሀገር አስተዳደር ኃላፊነትን ለመቀበል እንዲደርሱ ያደረጉትን ተወዳዳሪ የሌለው ተጋድሎ፤ የአገራችንም ሆነ የዓለም ታሪክ የተከበረውን ቦታ እንደሚሰጣቸው አያጠራጥርም።

በአሥራ ዘጠነኛው ክፍለ ዘመን መጨረሻ ላይ፤ አባታቸው ራስ መኰንን የአጐታቸው የአፄ ምኒልክ ልዩ መልዕክተኛ ሆነው ከአንድም ሁለት ጊዜ የእንግሊዝን፣ የፈረንሣይንና የጣልያንን አገሮች ሲጐበኙ፤ ለሥልጣኔ መሠረቱ ትምህርት መሆኑን የማየት ዕድል ስለአጋጠማቸው፤ ልጃቸው ተፈሪ ገና ከሕፃንነት ዕድሜያቸው ጀምሮ ሐረር በሚገኘው የፈረንሣይ ሚሲዮን እየተማሩ እንዲያድጉ አደረጉ። በዚህ በካቶሊክ ሚሲዮን በኩል ለተፈሪ መኰንን እና አብሮ አደጋቸው ለሆኑት ለእምሩ ኃይለሥላሴ የተለየ አስተማሪ ተመድቦላቸው የሚሰጣቸው የቀለም ትምህርት፤ የፈረንሣዊኛን ቋንቋ ለመናገርና መጻሕፍትን አንብቦ ለመረዳት ብቻ ሳይሆን፤ ስዋሰውን አጥንቶ ሐሳብን በጽሑፍ ከመግለጽ ደረጃ ለማድረስ ነበር።

የሚሲዮኑ መሪ የሆኑት ፈረንሣዩ ሞንሴኘር ዣሮሶ (JAROSSEAU) ተፈሪን ያወቁት ገና የስድስት ዓመት ልጅ በነበረ ጊዜ ሲሆን፤ ጨዋነቱንና ብልህነቱን በማየት፤ «.. ይህ ልጅ አንድ ቀን የአባቱን ግዛት መሾም ብቻ ሳይሆን፤ ምናልባትም ምኒልክ ለወራሽነት ቢመርጡት አይደንቀኝም ... » የሚል አስተያየት ሰንዝረው ነበር ይባላል። ራስ መኰንን፤ ልጃቸው ፈረንሣዊኛ እንዲናገርላቸው የፈለጉት፤ እሳቸው የአፄ ምኒልክ ልዩ መልዕክተኛ በመሆን ወደ አውሮፓ እየተላኩ ከየመንግሥታቱ መሪዎች ጋር በሚገናኙበት ጊዜ፤ ቋንቋ አለማወቃቸው እጅግ አድርጎ ስለቆጫቸው፤ ወደፊት ለብዙ ነገር ተስፋ ያሳደሩበት ልጃቸው፤ ቋንቋ

ተምሮ የተዘጋጀ እንዲሆንላቸው በማሰብ ነበር። ለትምህርቱ ጉዳይ ከራስ መኰንን አደራውን የተቀበሉት ፈረንሣዩ ቄስ ደግሞ፤ ወጣቱ ተፈሪ በፈረንሣዊኛ ማንበብና መረዳት ከሚችልበት ደረጃ ከደረሰ በኋላ፤ በአውሮፓው ዓለም የተደረገው የሥልጣኔ ዕድገት መሠረተ ታሪኩና ውጤቱ ምን እንደሆነ ለማወቅ እንዲችል፤ የተለየ ጥረት ያደርጉለት ነበር። ይኸውም፤

-- ከኤሌክትሪክ የሚመነጭ " ብርሃን" ማምረት ስለተቻለ፤ የቀን ጀምበር ከጠለቀ በኋላ፤ በጭለማው ሰዓት በኩራዝና በጧፍ መደናበር እንደተወገደ፤

-- በብረት ሐዲድ ላይ የሚሽከረከር ባቡር በመሠራቱ፤ የየገጠሩን ሕዝብ ለማገናኘትና የንግድ ሕይወቱን ለማንቀሳቀሻ ምን ያህል እንደጠቀመ፤

-- የስልክ የሽቦ መስመሮች በመዘርጋታቸው፤ የመንግሥቱን አስተዳደር ለማቀላጠፍ ብቻ ሳይሆን፤ ሕዝቡን እርስ በርሱ ለማገናኘትና ለማቀራረብ እንደተቻለ፤

-- አውቶሞቢሎችና አነስተኛ ተሽከርካሪዎች ተሠርተው በመቅረባቸው፤ ምን ያህል የመጓጓዣ ምቾትና ቅልጥፍና እንደተገኘ፤

-- ልዩ ልዩ የጦር መሣሪያዎች ተፈልስፈው የተሠሩት ዘመናዊዎቹ ታንኮችና መድፎች፤ ለውጭ ጠላት መቋቋሚያ የቱን ያህል አስተማማኞች ለመሆን እንደበቁ፤ ተፈሪ መኰንንን ለማስተማር የቀረቡ ጥናቶች ነበሩ።

በሠለጠነው ዓለም ከእነዚህ በቴክኒዎሎጂ በኩል ከተደረጉት እርምጃዎች ሌላ፤ በአስተዳደርም ረገድ በጥንታዊው ዘመን ከነበረው የባርነት የቅጥቀጣ አገዛዝ፤ በመጠኑ ወደተሻለው ፊውዳላዊ የገባር ጭቆና ሥርዓት ለመዛወር ምን ያህል ዘመን እንደወሰደ፤ ቀጥሎ ደግሞ፤ ከፊውዳላዊው ሥርዓት ወደ ዴሞክራሲያዊ አመራር ለመሸጋገር፤ ሕዝቡ ያደረገው የረዥም ዘመን ትግልና የከፈለው መሥዋዕትነት ምን ያህል እንደሆነ፤ ተፈሪን ለማስተማር ፈረንሣዩ ቄስ የተቻላቸውን ሁሉ ማድረጋቸው ይነገርላቸዋል። ምንም እንኳ በልጅነት ዕድሜና በተወሰነ የቋንቋ ችሎታ፤ እጅግ ውስብስብ የሆነውን የምዕራብን የሥልጣኔ ታሪክ በጥልቀት ለመረዳት አስቸጋሪ ቢሆንም፤ « ... **ወጣቱ ተፈሪ የተፈጥሮ ብልህነቱ ከፍ ያለና ብሩህ የሆነ አእምሮ ስላለው፤ በእርጋታ የምናስጠናውን ታሪክ አንዳንድ ጊዜ ከጠበቅነው በላይ ተረድቶት እናገኘዋለን ...** » ሲሉ ሞንሴኘር ዣሮሶ (JAROSSEAU) አስተያየታቸውን ሰጥተዋል። ተፈሪ መኰንን ዕድሚያቸው ደርሶ በሹመት ወደ ሥራ ኃላፊነት ከተዛወሩ በኋላ፤ በተለይም የሐረርጌ ጠቅላይ ገዥ ሆነው በቆዩበት በስድስቱ ዓመታት ውስጥ ከሞንሴኘር ዣሮሶ ጋር ባላቸው ቅርበት፤ ስለ ፈረንሳይ የሥልጣኔ ታሪክና ስለ ቀዳማዊ ናፖሊዮን መሪነት፤ ቢያንስ በቀን አንድ ሰዓት ጥናታቸውን ቀጥለው እንደነበረ ታውቋል።

ተፈሪ መኰንን፤ ከዚህ ሐረር ከሚገኘው የካቶሊክ ሚሲዮን መምህራኖችና በተለይም ከመሪው ከሞንሴኘር ዣሮሶ ባገኙት ትምህርት፤ ኢትዮጵያ የዘመኑን ጥበብ ተከትላ ሕይወቷን ለማሻሻል ብዙ ሥራዎች እንደሚጠብቋት ቢያውቁም፤ ከሠለጠኑት አገሮች የቱን ያህል ወደ ኋላ ቀርታ በሚያሳዝን ሁኔታ እንደምትገኝ በግልጽ ለመረዳት የቻሉት፤ አልጋወራሽ ሆነው፤ በ1916 ዓ.ም የአውሮፓን አገሮች በጐበኙ ጊዜ ነው። በዚህ አራት ወራት በፈጀው የባሕር ማዶ ጉዞአቸው ላይ፤ ብዙ

ሁኔታዎችን ከተመለከቱና ካጠኑ በኋላ፤ ኢትዮጵያ የመሠልጠን ዕድል የሚኖራት፤ ከአሁኑ ጀምሮ ልጆቿን በዘመናዊ ትምህርት እያስተማረች ለማዘጋጀትና፤ የባሕር በር መተላለፊያ አግኝታ ባላት አቅም ከውጭው ዓለም ጋር የንግድ ልውውጥ ለማድረግ ስትችል ነው በማለት፤ ከዚህ ቀደም አንዳንድ አዋቂዎች ያቀረቡላቸው ሐሳብ ትክክል መሆኑን በይበልጥ ለመረዳት ቻሉ።

የባሕር በር ለማግኘት፤ ቀደም ሲል እንግሊዞች በበርበራ፣ ፈረንሣዮች በጂቡቲ፣ ጣልያኖች በአሰብ በኩል፤ ከሦስት አንዳቸው መተላለፊያ እንዲከፍቱልን ስለተጠየቀ፤ መልሱን ከመጠበቅ በስተቀር ሌላ የሚደረግ ነገር አይኖርም። የትምህርቱ ጉዳይ ግን በጣም የሚያሳስብ ስለሆነ፤ የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት እንዲረዱን ጥያቄያችንን በአስቸኳይ ማቅረብ አለብን። ለማናቸውም የክብር ተከታዮቻችን ሆነው አብረውን የመጡት መሳፍንትና መኳንንት ተጠርተው፤ በእነሱ በኩል ለኢትዮጵያ የሚጠቅም ምን ዓይነት እርዳታ መጠየቅ እንደሚሻል፤ ሐሳባቸውን መስማት ያስፈልጋል በማለት፤ ሰኔ 6 ቀን 1916 ዓ.ም አልጋወራሽ ተፈሪ በፓሪስ የማረፊያ ሆቴላቸው ውስጥ ስብሰባ አደረጉ። « .. ለዚህ ጉብኝት ወደ አውሮፓ ከመምጣታችን በፊት፤ ኢትዮጵያ አገራችን ከዘመኑ ሥልጣኔ ርቃ እንደምትገኝ ባውቅም፤ ምን ያህል በጨለማ ውስጥ እንደምትኖርና፤ ከዚህም ጨለማ ወጥታ ብርሃን ለማግኘት ብዙ አቀበትና ቁልቁለት ተደቅኖባት እድካሚ የሆነ ውጣ ውረድ እንዳለባት በግልጽ አልታየኝም ነበር። አሁን ግን ችግራችን ምን ያህል ከባድ መሆኑንና ከዚህም ለመላቀቅ መድኃኒቱ ምን እንደሆነ ስለተረዳሁት፤ የዚህን የአውሮፓ አገሮች ጉብኝቴን ከመፈጸሜ በፊት፤ ለአገራችን አንድ ጠቃሚ የሆነ እርዳታ ሳልይዝላት መመለስ የለብኝም ብዬ ወስኛለሁ። ስለዚህ፤ እናንተም በየበኩላችሁ እንዳስተዋላችሁት ምን ዓይነት እርዳታ መጠየቅ እንደሚሻል ሐሳባችሁን ግለጹልኝ .... » ብለው፤ የክብር ተከታዮቻቸውን ጠየቁ። መሳፍንትና መኳንንት የተጠየቁትን ለመመለስ የአንድ ቀን ጊዜ ተሰጥቷቸው፤ እርስ በርሳቸው በመነጋገር ጉዳዩን አጥንተው ከተስማሙበት በኋላ፤ የአሥራ ሁለቱ የክብር ተከታዮች ተቀዳሚ የሆኑት ራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖት (የጐጃም ገዥ) በራሳቸውና በሰባቱ ጓደኞቻቸው ስም ሆነው የሚከተለውን ሐሳብ ሰጡ።

ከሁሉ አስቀድሞ አልጋወራሽ ሌት ተቀን የሚጨነቁበት ይኸ ሥልጣኔ የሚባለው ነገር እውነተኛ ትርጓሜው ምን ማለት እንደሆነ ለእኔም ለጓደኞቼም የተገለጠልን አልመሰለኝም። ሆኖም፤ አገራችን በሥልጣኔ ወደ ኋላ ቀርታለች እየተባለ በብዙ የሚነገርብን፤ ከፈረንጆቹ አኗኗርና ወግ ጋር፤ ከፈረንጆቹ የጦር መሣሪያ ሀብትና የሕንፃ ቤቶች ጋር፤ ከሚያሽከረክሯቸው መኪናዎችና ባቡሮች ጋር በማስተያየት ከሆነ፤ በእርግጥ በጣም የተለየን፤ እንዲያውም በጣም ሩቅ ነን ማለት ይቻላል። ነገር ግን የአንድ አገር ሥልጣኔ የሚለካው፤ በታሪኩና በባህሉ፣ በሃይማኖቱና በምግባሩ፣ በጨዋነቱና በቁም ነገሩ ከሆነ፤ እኛም በአገራችን ብዙ ነገሮች ስላሉን፤ ከፈረንጆቹ አንስናል ብለን ማዘንም መጨነቅም የለብንም። አሁን በምሳሌ፤ እዚህ ፈረንሣይ አገር ከመጣን ጀምሮ፤ ጋባዦቻችን ለእኔና ለጓደኞቼ ሲያሳዩን የሰነበቱት ሁሉ፤ አንዱም ለአገራችን ጠቃሚ ሆኖ አላገኘነውም። በየመንገዳቸው ላይ ከጥርብ ድንጋይ የተሠሩ ብዙ ፎቅ ቤቶች አንዱን ካንዱ እያቀጣጠሉ አጥር አስመስለው ገንብተዋል። ሕዝቡም በነዚሁ ፎቅ ቤቶች ውስጥ ተጨናንቆ እንደሚኖር አሳይተውናል። ይህንንም ያደረጉት ምናልባት የመሬት ጥበት ቢኖራቸው ይሆናል ብለን ገምተናል። የድሮዎቹ ነገሥታቶቻቸው የኖሩበትን ቤተመንግሥቶቻቸውን፣ የመኝታ አልጋዎቻቸውንና የማረፊያ መከዳዎቻቸውን፣ ሥዕሎቻቸውንና ጌጣጌጦቻቸውን አንድ በአንድ ማየት አለባችሁ ብለው ሲያደክሙን ሰንብተዋል። በከተማቸውም ውስጥ በየሠፈሩ ብዙ የሰው ሐውልቶች

ተከለዋል። ሁሉም የታሪክ ሰዎች ናቸው በማለት እያደነቁ አሳይተውናል። አንዳንዶቹም ግጥም ገጣሚዎች የነበሩ ናቸው ይሉናል። ታዲያ፤ ይኸ ሁሉ ለአገራችን ምን ጥቅም ይሰጣል ? .... ይልቁንስ፤ የጦር መሣሪያዎች የሚያወጡበትን ፋብሪካ ቢያሳዩን፣ የልብስና የጫማ ፋብሪካቸውን ብናይላቸው፤ በእርሻም በኩል በየዓመቱ ሁለት ሦስቴ እናመርታለን እያሉ የሚፎክሩት፤ መሬታቸውን በምን አኳኋን ቢያርሱትና ምን ዓይነት ዘር ቢዘሩበት መሆኑን ቢያሳዩን፤ ምናልባት አንዳንድ ጠቃሚ የሆነ ነገር እናገኝበት ነበር። ይህ ሁሉ አልሆነም። እነሱ የሚያሳዩን ሌላ፤ እኛ ማየት የሚያምረን ሌላ ሆኗል።

## ልዑል ጌታችን ሆይ፤

እኔና ጓደኞቼ እንድናጠናው የጠየቁንን ከማቅረባችን በፊት፤ በዚህ በጉብኝታችን ጊዜ በተለይ በፈረንሣይም ሆነ በቤልጊክ አገሮች ያየናቸውንና ያሳደሩብንን ስሜት ሳንደብቅ እውነቱን ገልጠን የተናገርነው፤ ልዑል ጌታችን እንዲያውቁት ለማለት ነው እንጂ፤ ለአገራችን ለኢትዮጵያ የሚጠቅማትንና የሚጐዳትን ከርስዎ የተሻለ የሚያውቅ እንደሌለ ከልባችን እናምናለን። አሁንም፤ ዛሬም ሆነ ነገ፤ ከፈረንጆቹ ጋር ለሚያስፈልገን ግንኙነት ልዑል ጌታችን እንደሚደክሙበት፤ የእነሱን አኗኗር፣ የእነሱን ጥበብ፣ የእነሱን ሐሳብ መከተል፤ ለአገራችን ይጠቅማታል ከተባለ፤ እነሱ ያሏቸው ጥሩ ጥሩዎቹ ነገሮች እየተመረጡ፤ ገንዘብ እየከፈልናቸው አገራችን መጥተው እንዲሠሩልን ማድረጉ የተገባ ይሆናል። ነገር ግን ለእነሱ የሚከፈላቸው የድካም ዋጋ ገንዘቡ በወርቅ ተተምኖ ስለሆነ፤ ወጭው ለመንግሥታችን የሚከብድ መሆኑ አይጠረጠርም። ስለዚህ፤ የፈረንጆቹ መንግሥታት በወዳጅነታችን እርዳታ አድርገው ለሚያስፈልጉት ሥራዎች ሁሉ ወጭዎቹን እነሱ እንዲከፍሉልን መጠየቁ ነውር አይሆንም። እነሱም አንድ ቀን ከእኛ የሚያስፈልጋቸው ነገር ቢኖር፤ ውለታቸውን እንመልሳለን። በዚህ ጉዳይ እኔና ጓደኞቼ በሰፊው ከተወያየንበት በኋላ፤ ልዑል ጌታችን በጠየቁን መሠረት የፈረንጆቹ መንግሥታት ቢረዱን ጠቃሚ ናቸው የሚባሉት ነገሮች፤ ከዚህ ቀጥሎ የምንዘረዝራቸው ቢሆኑ ይሻላል ብለን ተስማምተናል።

፩ኛ/ የውጭ ጠላትን የምንቋቋምበትና በአገራችን ውስጥ ወንበዴንና ቀማኛን የምናጠፋበት የጦር መሣሪያና የጥይት ፋብሪካ እንዲያቆሙልን፤

፪ኛ/ የጨርቃ ጨርቆችና በተለይም የብርድ ልብስ ፋብሪካ እንዲያቆሙልን፤

፫ኛ/ በከብት እርባታና በወተት በኩል፤ እነሱ እንደሚነግሩን ከላሞቻቸው እያንዳንዷ በቀን እስከ ሠላሳ (30) ዋንጫ ትታለባለች ይላሉ። ወይፈኖቹም ከተወለዱ ከአንድ ዓመት ተኩል በኋላ፤ በአራትና በስድስት ወራት ውስጥ ይደልባሉ ብለዋል። ይህ እውነት ከሆነ፤ እነሱ ወደ አገራችን መጥተው የዚህን የእርባታ ጥበባቸውን እንዲያሳዩን ማድረጉ ጠቃሚ ይሆናል። መችም ልዑል ጌታችን እንደሚያውቁት፤ ለፈረንጅ ልብንና አገርን ገልጦ ማሳየት አደጋ ቢኖረውም፤ ለጊዜው በእነዚህ በሦስቱ ዋና ዋና ጉዳዮች እርዳታ እንዲያደርጉልን፤ ከአሥሩ ሁለታችን የክብር ተከታዮች ውስጥ፤ እኛ ዋና ዋና የሆንነው ስምንቶቹ ተስማምተን፤ ይህን ሐሳብ ስናቀርብ፤ አራቱ የክብር ተከታዮች ከእኛ አፈንግጠው የተለየ ነገር አለን ብለዋል። ይህንንም እነሱ ራሳቸው ለልዑል አልጋወራሽ

ቢያቀርቡ እኛን አይከፋንም ሲሉ፤ የመሳፍንቶቹ ተቀዳሚ በራሳቸውና ስማቸው ቀጥሎ በተዘረዘረው ጓደኞቻቸው ስም ሆነው አስተያየታቸውን አቀረቡ።

1. ራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖት — የጐጃም ገዥ
2. ራስ ሥዩም መንገሻ — የትግሬ ገዥ
3. ደጃዝማች ሙሉጌታ ይገዙ — የምኒልክ ሚኒስትር (ኋላ ራስ)
4. ደጃዝማች ኃይለሥላሴ አባይነህ — የራስ እምሩ አባት
5. ደጃዝማች ገሠሠ ወልደሀና — የእቴጌ ጣይቱ ዘመድ
6. ደጃዝማች ወንድወሰን ካሣ — የራስ ካሣ ልጅ
7. ሊጋባ ወዳጄ ውቤ — የቤተመንግሥቱ ሊጋባ
8. አቶ ሣህሌ ፀዳሉ — (ኋላ ብላቴን ጌታ የትምህርት ሚኒስትር)

ከእነዚህ ከአብዛኞዎቹ ታላላቅ ሰዎች አስተያየት ጋር ያልተስማሙት አራቱ ሰዎች ያቀረቡት ሐሳብ፤

"የኢትዮጵያ ወዳጆች ናቸው የተባሉት ፈረንሣዮችም ሆኑ እንግሊዞች፤ በአገራችን ላይ ብዙ ወቀሳ ሲያወርዱ የኖሩት፤ ዘመናዊ ትምህርት እንዲስፋፋ ባለማድረጋችሁ፤ አገራችሁ ከሥልጣኔ እጅግ ወደ ኋላ ቀርታለች እያሉ ነው። አሁን ግን በልዑል አልጋወራሻችን የሚመራው መንግሥት ኢትዮጵያን ለማሠልጠን የቆረጠ ስለሆነ፤ ለዚህ አስፈላጊ የሆነውን ትምህርት ልጆቻችን እንዲማሩ፤ እነዚህ ወዳጆቻችን ናቸው የተባሉት አገሮች፤ ለተማሪ ቤቶች ሕንፃ ማሠሪያና ለውጭ አገር አስተማሪዎች መቅጠሪያ የሚሆን እርዳታ እንዲሰጡን መጠየቅ፤ ከሁሉ ቅድሚያ የሚሰጠው ነው " የሚል ነበር። እነዚህም አራቱ ሰዎች፤

-- ደጃዝማች ናደው አባ ወሎ የኢሉባቡር ገዥ (ኋላ ራስ) አውሮፓን ብዙ ጊዜ የጐበኙ፣

-- ደጃዝማች ገብረሥላሴ ባሪያ ጋብር የአድዋ ገዥ፤ ጣልያንኛ የተማሩና የዘመኑን ሥልጣኔ የሚከተሉ፤

-- ብላታ ሕሩይ ወልደሥላሴ ያገራቸውንና የሠለጠነውን ዓለም ታሪክ የሚያውቁ፤ (ኋላ የቀ.ኃ.ሥ. የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር)

-- ልጅ መኰንን እንዳልካቸው ፈረንሣዊኛ የተማሩ፤ (ኋላ የቀ.ኃ.ሥ. ጠቅላይ ሚኒስትር) ናቸው።

አልጋወራሽ ተፈሪ፤ ስምንቱ መሳፍንትና መኳንንት ከሰጧቸው ምክር ይልቅ፤ እነዚህ አራቱ ሰዎች ያቀረቡላቸው ሐሳብ ከእሳቸው ፍላጐት ጋር የተገጣጠመ ስለሆነላቸው፤ **ከፈረንሣይና ከእንግሊዝ መንግሥታት የሚጠየቀው እርዳታ ለትምህርት ማስፋፊያ ብቻ እንዲሆን ወሰኑ።** በዚህ መሠረት፤ ለሁለቱ አገሮች ባቀረቡት ማመልከቻ፤ « ... ኢትዮጵያን ወደ ሥልጣኔ ለማሻገር መድኃኒቱ ትምህርት መሆኑን ወዳጆቻችን የሆናችሁት መንግሥታት ሁሉ በየጊዜው የሰጣችሁንን ምክር በደስታ አስታውሳለሁ። ለዚህም፤ ከአሁኑ ጀምሮ የኢትዮጵያን ልጆች ዘመናዊውን የሥልጣኔ ትምህርት በፈረንሣዊኛና በእንግሊዝኛ ለማስተማር ቆርጬ መነሣቴን እንድታውቁልኝ እፈልጋለሁ። ይህንንም ሐሳቤን ከግቡ ለማድረስ እንድችል፤ **እንደኛ/ ለተማሪ ቤቶቹ ሕንፃዎች ማሠሪያ፣ ሁለተኛ/**

ከፈረንሣይና ከእንግሊዝ አገሮች እየተመረጡ ለሚቀጠሩት አስተማሪዎች ደሞዝና የማስተማሪያ መጻሕፍቶች መግዣ እንድትረዱኝ አጥብቄ አመለክታለሁ …. ›› ሲሉ ከፍ ያለ የልመና ደወል አሰሙ።

ተፈሪ መኰንን ይህንን ልመና ሲያቀርቡ፤ የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት የጠየቁትን ሁሉ በቶሎ የሚፈጽሙላቸው መስሏቸው ብዙ ተስፋ አድርገው ነበር። ነገር ግን ምን ይሆናል ? በኮሎኒያሊስቶቹ መሠረታዊ ፖሊሲ፤ የአፍሪካ ሕዝብ በቅኝ ገዥዎች አስተዳደር ተይዞ መከራን በሚቀበልበት ዓለም ውስጥ፤ ኢትዮጵያ ብቻዋን የነፃነት ፋና እያበራች በመቆየቷ አንድ ትልቅ ፕሮብሌም መሆኗ እየታያቸው፤ ከዚህ በላይ ደግሞ የሥልጣኔ ዕድገቷን ለማፋጠን የሚያስችላትን እርዳታ እንድታገኝ በምንም ምክንያት አይፈልጉም። እንደ እውነቱ ከሆነ፤ አልጋወራሽ ተፈሪ፤ ኢትዮጵያን ለማሻሻል ተማሪ ቤቶች ሥሩልን ! ልጆቻችንን አስተምሩልን ! የሚል ልመና ከማቅረብ ይልቅ፤ በሕዝባችን ዘንድ ታዋቂነትና ተደማጭነት ላላቸው መሳፍንቶቻችንና መኳንንቶቻችን፤ ዘመናዊ የሆኑ ቪላዎች ሥሩልን ! …. አውቶሞቢሎች ግዙልን ! ….. ብለው ቢጠይቁ ኖሮ፤ በደስታ ይፈጽምላቸው ነበር። ይህንንም የሚያሰኘው፤ ኮሎኒያሊስቶቹ በአፍሪካ ውስጥ በጉልበት የወሰዷቸውን አገሮች ለዘለዓለሙ ቅኝ አድርገው በሰላም ለመኖር እንዲችሉ፤ የየአገሩን ባላባትና የሕዝብ ተጠሪዎች ናቸው የሚባሉትን ጥቂቶች ሰዎች እየደለሉ ለማኖር የሚያደርጉትን ቸርነት በማየት ነው። በዚህም አኳኋን፤ ኮሎኒያሊስቶቹ ምንም እንኳ እንደ አፍሪካ አገሮች በኢትዮጵያ ውስጥ ምንም ዓይነት ይዞታ ባይኖራቸውም፤ የፊውዳላዊን ሥርዓት ከሚከተሉት መሳፍንት ጋር መቀራረብ፣ አንድ ቀን ሊጠቅመን ይችላል ብለው ስለሚያስቡ፤ ለአገሪቱ የሥልጣኔ ዕድገት የሚጠቅም እርዳታ ከመስጠት ይልቅ፤ ለእነዚህ ሰዎች ምቾትን መለገስ እንደሚመርጡ ማመን ይቻላል።

እንግዲህ፤ አልጋወራሽ ተፈሪ በዚህ በአውሮፓው ጉብኝታቸው፤ ከታላላቆቹ መንግሥታት የጠየቋቸውን የባሕር በር የማግኘት ጉዳይ ሆነ የተማሪ ቤቶች መሥሪያ፤ አንድ የተጨበጠ ነገር ሳይሰጧቸው ቀሩ። ፕሮግሬሲፍ በሆነው አቋምዎ አገርዎን ወደተሻለ አስተዳደር ለመምራት የሚያደርጉትን ጥረት እንደግፋለን በማለት ሲደልሏቸው የኖሩት ሁሉ፤ ጥያቄዎን አጥንተን መልሱን ወደፊት እናስታውቅዎታለን ከሚል ቃል አላለፉም። ስለዚህ፤ ተፈሪ መኰንን ለአገሬ አንድ ነገር ሳልይዝላት መመለስ የለብኝም ብለው ብዙ ተስፋ እንዳደረጉት፤ በመጨረሻው ምንም ሳያገኙ ባዶ እጃቸውን መመለሳቸው እጅግ አድርጎ አሳዘናቸው።

ይሁን እንጂ፤ ተፈሪ መኰንን በዚህ አራት ወራት በፈጀው የባሕር ማዶ ጉዞአቸው፤ ከታላላቆቹ መንግሥታት የጠየቁትን እርዳታ ባያገኙም፤ የአውሮፓው ዓለም የደረሰበትን የእድገት ደረጃ አተኩረው ከተመለከቱ በኋላ፤ የወደፊቷ ኢትዮጵያ፤

አንደኛ/ ከዚህ ከምትኖርበት ከጨለመው ዓለም ለመውጣትና የሥልጣኔ ብርሃን ለማግኘት፤ ዘመናዊውን ትምህርት ለማስፋፋት ቅድሚያ ከመስጠት በስተቀር፤ ሌላ መድኃኒት እንደሌላት፣

ሁለተኛ/ የሥልጣኔውን ጉዳና በመከተል አንዳንድ የአስተዳደር መሻሻል እያደረገች እርምጃዋን ካላሳየች፤ አሁን ባለችበት ደረጃ ነፃነቷን ይዛ ለመቆየት ትልቅ ችግር እንደሚሆንባት፣

ግልጽ በሆነ መንገድ ለመረዳት ችለዋል። በዚህም መሠረት፤ ከሁሉ አስቀድሞ ኢትዮጵያ ባላት አቅም ሁሉ ተጣጥራ ዘመናዊ ትምህርት ቤቶችን ለማስፋፋት ጊዜ የማይሰጥ ግዴታዋ መሆን አለበት፤ የሚል ሐሳብ ይዘው ወደ አገራቸው ተመለሱ።

ከአራት ወራት ጉዞ በኋላ፤ አዲስ አበባ በገቡ በጥቂት ሳምንታት ውስጥ የመጀመሪያው እርምጃቸው፤ መንግሥት ከመሬት ግብርና ከልዩ ልዩ ታክስ ከሚሰበሰበው ገንዘብ ለአገር መከላከያና ለክብር መጠበቂያ ከሚያስፈልገው ወጪ ቀጥሎ፤ ዘመናዊ ትምህርት ቤቶችን ለማቋቋሚያና ወጣቶችን በብዛት ለማስተማሪያ እንዲሆን፤ የንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱንና የታላላቆቹን ሚኒስትሮች ድጋፍ መጠየቅ ነበር። አልጋወራሹ በአውሮፓው ጉብኝታቸው ላይ በተለይ በጣልያን አገር ከሮማው ፓፓ ጋር በሰፊው ተገናኝተው ቡራኬ ሲቀበሉ ሰንብተው ነበር እየተባለ ውስጥ ውስጡን የሚነዛው ወሬ ሳይበርድ፤ ለኢትዮጵያ የፈረንጅ ትምህርት ቤቶችን በብዛት ማቋቋም ያስፈልጋል ሲሉ ያቀረቡትን ሐሳብ፤ እንኳንስ ሙሉ በሙሉ፤ በከፊልም ቢሆን የሚደግፋቸው ሳያገኙ ቀሩ። በታላላቆቹ አስተያየት በአገራችን የውጭ አገር ትምህርት መስጫዎችን ማብዛት ለካቶሊክ ሃይማኖት ዕድል መስጠት ነው የሚል ስለሆነ፤ የተፈሪ መኰንንን ሐሳብ ማዳመጥ አልፈለጉም። አገሬን ለማሻሻል የሚያስፈልገኝን እርዳታ አይነፍጉኝም ብለው እምነት ያሳደሩባቸው ታላላቆቹ የአውሮፓ መንግሥታት በመጨረሻው ቅር እንዳሰኛቸው ሁሉ፤ በአገራቸውም ውስጥ ከሐሳባቸውና ከዕቅዳቸው ጋር የሚተባበር በማጣታቸው የከበደ ሐዘን ሆነባቸው። ሆኖም ከጠዋቱ ያመኑበትን ከግቡ ለማድረስ፤ ብርቱ የመንፈስ ጥንካሬ ስለነበራቸው፤ እርምጃቸውን ከመቀጠል ወደ ኋላ አላሉም።

ለጉብኝት ወደ አውሮፓ ከመሄዳቸው በፊት በግል ገንዘባቸው ለማቋቋም የጀመሩትን የዘመናዊ ትምህርት ቤት ሕንፃ፤ ከጉዞአቸው ሲመለሱ መሠረቱ ሲጣል ከነበረው መጠን የበለጠ ትልቅ ሆኖ እንዲሰፋና ተማሪዎችን በብዛት ለመቀበል እንዲችል አሠርተው፤ ሚያዝያ 19 ቀን 1917 ዓ.ም ተመርቆ እንዲከፈት አደረጉ። "ተፈሪ መኰንን" ተብሎ በስማቸው የተቋቋመውን ይህን ተማሪ ቤት መርቀው በከፈቱበት ቀን፤ መኳንንትና ሚኒስትሮች የጦር አለቆችና ታላላቅ ሰዎች፤ የውጭ አገር መንግሥታት ዲፕሎማቶች በተገኙበት፤ የተማሪ ቤቱ መምህራኖችና ተማሪዎች በተሰለፉበት፤ አልጋወራሽ ተፈሪ ያደረጉት ንግግር በኢትዮጵያ ዘመናዊ የትምህርት ታሪክ ላይ የተከበረ ቦታ የሚሰጠው ስለሆነ፤ ዋና ዋናዎቹን ፍሬ ነገሮች አተኩሮ ማየት የሚያስፈልግ ይሆናል።

1. ….. ኢትዮጵያ ከማንም አገር ከአውሮፓም ሆነ ከእስያ፤ ራሷን ችላ በመኖር ቀደምትነት ያላትና፤ ነፃነቷን ሳታስነካ እየተጋደለች ለብዙ መቶ ዓመታት መቆየቷን፤ ገናናው ታሪኳና ባህሏም እጅግ የሚከበር መሆኑን፤ እንኳንስ እኛ ኢትዮጵያውያኖች ቀርተን፤ የውጭውም ዓለም በመጽሐፍ ሆነ በቃል ንግግር አድናቆቱን ያልገለጸ አይገኝም። ይሁን እንጂ፤ ዛሬ በአለንበት ዘመን፤ "ኢትዮጵያ እንዲህ ነበረች" "ኢትዮጵያ እንዲህ ነች" እያሉ መናገር ምን ይጠቅማል ? ብሎ ማሰብ አስፈላጊ ሆኗል።

2. …. የዛሬው ዓለም በሥልጣኔ ገስግሶ ኑሮውንና ጤናውን እያሻሻለ ከፍተኛ ደረጃ ላይ የደረሰ ስለሆነ፤ ኢትዮጵያ ከዚህ ሁሉ ርቃ፤ በጥንታዊው ታሪኳና ባህሏ ብቻ ተመክታ መኖር እንደማትችል በግልጽ የምንገነዘብበት ጊዜ ላይ ደርሰናል። ስለዚህም፤ የአገራችን የኢትዮጵያ ልጆች በዘመናዊ ትምህርት እያደጋችሁ፤ ኢትዮጵያ እንድትሠለጥንና እንድትለማ ብዙ ድካምና ብዙ ሥራ እንደሚጠብቃችሁ ማወቅ አለባችሁ።



የተፈሪ መኰንን ት/ቤት፤ ቀ.ኃ.ሥ በግል ገንዘባቸው የሠሩት፤ (ፎቶ ኢ.ጥ.ም.ተ)

3. .... አገሬን እወዳለሁ። አገሬን አፈቅራለሁ። የማይል የለም። ነገር ግን አገር በጭንቅ ላይ ስትገኝ አንድ ቁም ነገር ተጣጥሮ ከመሥራት፣ የአገርን ፍቅር በንግግር እያጠገቡ መቆየት፣ ለዘለቄታው ፍሬ የሚሰጥ አይሆንም። ለአገራችን የሥልጣኔ ዕድገት መሠረታዊ ችግሯና ጭንቋ የትምህርት እጦት ነው። ይህንኑም በማሰብ፣ ታላቁ ንጉሠ ነገሥት ዳግማዊ ምኒልክ፣ ኢትዮጵያን በዕውቀት ለማሠልጠን የውጭ አገር ትምህርት የሚሰጥበት ተማሪ ቤት ማቋቋማቸውን ሁላችሁም ታውቃላችሁ። እኔም ባለኝ አቅም በግል ገንዘቤ ይህን ትምህርት ቤት ሠርቼ እንድትማሩበት የሰበሰብኳችሁ፣ ዘመኑ የሚጠይቀውን ዕውቀት ገብይታችሁ፣ ለአገራችሁ ዕድገት ረዳት ሆናችሁ እንድትደርሱላት ብዬ ነው።

4. ..... አገራችን ኢትዮጵያ ወደ ሥልጣኔ ለምታደርገው ጉዞ እናንተ ብቻ በቂ አትሆኑም። የእናንተን ያህል ብዙ ሺህ ጊዜ እጥፍ ያስፈልጓታል። በሥልጣኔ እጅግ የተራመዱት የአውሮፓ አገሮች፣ በዛሬው ሰዓት የተማሪዎቻቸውን ቁጥር በብዙ መቶ ሺህ እየደመሩ የሚናገሩት፣ ቀደም ሲል እነሱም እንደ እኛው ቁጥሩን ከአንድና ከአሥር ጀምረው ነው። ስለዚህ፣ እናንተም ዛሬ ቁጥራችሁ መቶ እንኳ ባይደርስም፣ በየጊዜው እየጨመራችሁ፣ በጥቂት ዓመታት ውስጥ መቶ ጊዜ እጥፍ እንደምትሆኑ አይጠረጠርም።

5. .... አሁን ይህች ተማሪ ቤት አንድ ትንሽ ምሳሌ ነች። ግን ትልቅ ፍሬ ትሰጣለች ብዬ እተማመንባታለሁ። ይህችም ቀን ዛሬ ለእኔ ምን ያህል የደስታ ቀን እንደሆነች፣ ልቤና ፈጣሪዬ ብቻ ነን የምናውቀው። እግዚአብሔር ፈቃዱ ሆኖ ዕድሉን ቢሰጠኝ፣ የዚችን ተማሪ ቤት መከፈቷንና ሥራ መጀመሯን አይቼ እጅግ ደስ እንዳለኝ ሁሉ፣ በዚች ተማሪ ቤት እንድትማሩልኝ የሰበሰብኳችሁ ልጆች ደግሞ፣ ትምህርታችሁ ፍሬ ሰጥቶ አገራችሁን ስትረዱ ለማየት እንዲያበቃኝ ፈጣሪዬን አጥብቄ እለምነዋለሁ።

6. .... እናንተንም በዚህ በልጅነት ዕድሜያችሁ ተቀብላ፣ የዕውቀት ምግብ እየሰጠች የምታሳድጋችሁ ይህች ተማሪ ቤት፣ ለአገራችን የዕድገት መሣሪያ ስለሆነች፣ ወደፊት ተስፋፍታ ብዙዎቹን ወጣቶች ለማስተማር እንድትበቃ፣ እናንተ የዛሬ ልጆች፣ የነገ ፍሬዎች፣ ለቁም ነገር በምትደርሱበት ጊዜ፣ እርዳታችሁ እንዳይለያት፣ ዘወትር እንድታስቧት፣ አጥብቄ እለምናችኋለሁ .... ››

እንግዲህ ! ከዚህ በላይ እንደታየው፣ ተፈሪ መኰንን ኢትዮጵያን ከጨለማ ወደ ብርሃን ለማሻገር በሚያደርጉት ጥረት፣ ፍቱን የሆነው መድኃኒት ትምህርት ብቻ መሆኑን፣ ምን ያህል እንደአሰቡበት፣ ምን ያህል እንደተጨነቁበት፣ ምን ያህል ለመሥራት ቆርጠው እንደተነሡ፣ በሚገኘውም ውጤት ምን ያህል ተስፋ እንደሚያደርጉ፣ ከልብ የመነጨ የጋለ ስሜታቸውን ገልጸዋል። ‹‹ የዚህ ተማሪ ቤት መከፈት ደስ እንዳለኝ፣ እናንተንም ለማስተማር የሰበሰብኳችሁ ልጆች፣ ትምህርታችሁ ፍሬ ሰጥቶ አገራችንን ለማገልገል ስትደርሱ ለማየት እንዲያበቃኝ፣ ፈጣሪዬን እለምነዋለሁ። ›› ብለው ጥልቅ ምኞታቸውን እንደገለጹት፣ በዘመናቸው ያስተማሯቸው ሁሉ ረዳቶቻቸው ለመሆን እንደበቁ፣ ወደፊት የመንግሥታቸውን ታሪክ እየተከተልን ስንሄድ በየጉዳዩ እናገኘዋለን።

የተፈሪ መኰንን ተማሪ ቤት ተመርቆ ሥራውን ከጀመረ በኂላ፣ ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ ተቀዳሚ በመሆን፣ የጦር ሚኒስትሩ ፊታውራሪ ሀብተጊዮርጊስና ሌሎችም ታላላቅ መኳንንት በስማቸው ይህንኑ የመሰለ ልዩ ልዩ ዘመናዊ ትምህርት ቤቶች አሠርተው ለኢትዮጵያ ልጆች ዕውቀት መቅሰሚያ ያበረክታሉ ተብሎ በተስፋ ተጠብቆ ነበር። ነገር ግን፣ የተፈሪ መኰንን ተማሪ ቤት መከፈት ዝና የተሰጠው፣ ለኢትዮጵያ ሥልጣኔ የሚበጀውን ሁሉ ለመቀበል ዝግጁ ነን በሚሉት የአልጋወራሹ ደጋፊዎች በሆኑት ተራማጆችና እንዲሁም የካቶሊክ ዕምነት ተከታዮች በሆኑት ዘመናዊ ሰዎች ዘንድ ስለሆነ፣ ቤተክህነቱና ወግ አጥባቂ የሆነው የመኳንንቱ ቤተሰብ የሚያሳየው ተቃውሞ እጅግ የበረታ ሆነ። ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱም ምንም እንኳ በአገራችን የውጭ አገር ትምህርት የሚሰጥበትን ተማሪ ቤት ለማቋቋም፣ የመጀመሪያውን እርምጃ የወሰዱት አባታቸው አፄ ምኒልክ ቢሆኑም፣ በአልጋወራሽ ተፈሪ ላይ በሚነዛው ሐሜታ ምክንያት፣ ለዘመናዊ ትምህርት ማስፋፊያ ረዳት ሆነው መታየትን አልፈለጉም። ሌሎቹም እንደ ፊታውራሪ ሀብተጊዮርጊስ የመሳሰሉት ታላላቅ መኳንንት አስተያየታቸው ከንግሥቲቱ የተለየ መሆን አልቻለም። አልጋወራሽ ተፈሪ የቤተክህነቱን ተቃውሞ ለማስታገስ፣ ለውጭ አገር ትምህርት መማሪያ በሚቋቋሙት ተማሪ ቤቶች ሁሉ፣ የአገራችን የቅዱሳት መጻሕፍትና የወንጌል ትምህርት በፕሮግራም ተመድቦ ተማሪዎቹ እንዲማሩ አደርጋለሁ የሚል ቃል ሰጥተው ነበር። ይህም ቢሆን፣ « .... ተማሪ ቤቶቹ የቆሙት ለፈረንጆች ትምህርት መስጫ ተብሎ ስለሆነ፣ ሰፊው የአገራችን ትምህርት በቅዱሳት መጻሕፍትና በወንጌል ንባብ ብቻ መወሰኑ አይጠቅምም ..... » በማለት፣ ቤተክህነቱ የራስ ተፈሪን ሐሳብ ለመቀበል ፈቃደኛ አልሆነም። ይልቁንም በአልጋወራሹ ላይ ተቃውሞአቸውን ያጠነከሩት፣ የቤተክህነትና የወግ አጥባቂ ወገኖች፣ በዳግማዊ ምኒልክና በተፈሪ መኰንን ትምህርት ቤቶች ለመማር የተመዘገቡትን ወጣቶችና ቤተሰቦቻቸውን እየቀረቡ፣ « .... በፈረንሣዊኛና በእንግሊዝኛ ቋንቋዎች የሚሰጡት ትምህርቶች፣ የተዋህዶ ሃይማኖትን ወደ ካቶሊክ ዕምነት ማስለወጫ ናቸው ..... » የሚል ስብከት ነዙባቸው። በመስከረም 1918 ዓ.ም የዓመቱ የትምህርት ፕሮግራም ሲከፈት፣ ተመዝግበው ከነበሩት ተማሪዎች ግማሾቹ ሳይመጡ ቀሩ።

የየመኳንንቱና የታላላቆቹ ቤተሰቦች ልጆቻቸውን ተማሪ ቤት ለመላክ ድሮውንም ቢሆን ስለማይፈልጉ፣ የተፈሪ መኰንን ተማሪ ቤትም ለእነሱ ቦታ አዘጋጅቶ አልጠበቃቸውም። የእነሱ ልጆች ከትልቅ የተወለዱ በመሆናቸው፣ በአስተዳደግና በኑሮ ምቹነት የሚያገኙት ዕውቀት ከሁሉ የበለጠ ነው ብለው ስለሚያምኑ፣ ወደ ተማሪ ቤት አለመምጣታቸውም ሆነ መቅረታቸው፣ የሚያሳስብ አልነበረም። ነገር ግን፣ ራስ ተፈሪንና ረዳቶቻቸውን ያስደነገጣቸው፣ የተቋቋሙት ተማሪ ቤቶች እንዲዘጉ በተንኮለኞቹ የተነዛው ፕሮፓጋንዳ፣ የደሀውን ቤተሰብ ጭምር የማረከ በመሆኑ ነው። በዚያን ጊዜ ራስ ተፈሪ፣ ከአልጋወራሽነት ሌላ የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴ ቢሆኑም፣ ሃይማኖትን ተመርኩዞ የመጣባቸውን ተቃውሞ በሥልጣን ኃይል ሊቋቋሙት እንደማይችሉ ስለተረዱት፣ ሌላ መንገድ መፈለግ ግዴታ ሆነባቸው። ይኸውም፦

1ኛ/ ቤተክህነት ስለአደረገባቸው ተቃውሞ ምንም ዓይነት የመከላከያ መልስ ሳያቀርቡ፣

2ኛ/ ስለ መኳንንት ልጆች መማርና አለመማር ምንም ዓይነት አስተያየት ሳይሰጡ፣

« .... ከድሃው ቤተሰብ የተወለዱት ልጆች ትምህርታቸውን በትጋት ለመከታተል ፍላጐት ሳላቸው፣ በየወሩ የመኖሪያ ደሞዝ ይቆረጥላቸዋል ..... » የሚል መግለጫ አወጡ። በዚህ ጊዜ የድሀ ቤተሰቦች የሆኑት ሁሉ፣ በውጭ አገር ቋንቋ የሚሰጠው ትምህርት፣ የሃይማኖት ጠንቅ ነው እየተባለ የሚነገረው እውነት ቢሆንም ባይሆንም፣ ለየተማሪዎቹ በየወሩ የሚከፈላቸው ደሞዝ ለኑሮአችን መደገፊያ ይሆነናል ብለው በመጓጓት፣ ልጆቻቸውን ወደ ተማሪ ቤት ለመላክ ሁሉም ተሽቀዳደሙ። እንደሚታወቀው፣ በጥንታዊውም ሆነ በዛሬው ዘመን ገንዘብ የማይማርከው ስለሌለ፣ ይህ የተፈሪ መኰንን የተማሪዎች መርጃ ዕቅድ በተገለጸ ወር ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፣ የዳግማዊ ምኒልክና የተፈሪ መኰንን ተማሪ ቤቶች ካላቸው አቅም በላይ ብዙ ተማሪዎች ቀረቡላቸው። ይህም ውጤት በቶሎ በመታየቱ፣ ለተፈሪ መኰንን ከጠበቁት በላይ ትልቅ ደስታ ሆነላቸው።

በየትምህርት ቤቱ ለመመዝገብ በብዛት የቀረቡትን ተማሪዎች ሁሉ በተቻለ መጠን ቦታ ለማስያዝ፣ አልጋወራሽ ተፈሪ ከመምህራኖቹ ጋር ሆነው በሚደከሙበት ጊዜ፣ መቸውንም የማይተኙላቸው ተቃዋሚዎቻቸው እንደገና ሌላ ችግር አጠመዱባቸው።

መሳፍንቱና መኳንንቱ ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ ዘንድ እየሄዱ፣ « ..... የሃይማኖታችንና የባህላችን ፀር መሆኑ የታወቀው የፈረንጅ ትምህርት መስፋፋቱ ከፍ ያለ ጭንቅ ላይ ሲጥለን፣ አሁን ደግሞ መልካም ምግባር ያላቸውን ልጆቻችንን እያታለሉ ወደዚሁ ተማሪ ቤት ለመክተት፣ ከመንግሥቱ ሳጥን እንደ ሠራተኛ በየወሩ ደሞዝ እንዲከፈላቸው መደረጉ፣ እጅግ የሚያስገርምና የሚያሳዝን ሆኖብናል .... » በማለት፣ በአልጋወራሹ ላይ ከፍተኛ ቅሬታቸውን አመለከቱ። እንደዚሁም በእነዚሁ በታላላቆቹ ሰዎች አነሣሽነት፣ የቤተክህነት ኃላፊዎችም የተቃውሞ እንቅስቃሴ አደረጉ።

-- ኧረ ለመሆኑ ይኸ ሁሉ የት ነው የሚያደርሰን ?
-- አገራችን የተከበረ ባህሏና ታሪኳ የሚጠነክርበትን ሳይሆን፣ የሚጠፋበትን መንገድ እንድትከተል አልተደረገም ወይ ?

-- አገራችን ልጆቿን በትምህርት ለማነፅ የሚያስችሏትን፣ በሊቃውንቶች የተመሰከሩ ብዙ የባህል ጥበቦች እያሏት፣ የጠላቶቻችንንና የአጥፊዎቻችንን ተንኮል ለመገብየት ለምን ትደክማለች ?

-- ለአገራችን በውነት የሚታሰበው፣ ዕውቀትን ለማበልጸግና ትምህርትን ለማስፋፋት ከሆነ፣ ለጠላቶቻችን ተንኮል ወጪ ከመከንዳት፣ አማርኛና ግዕዝን፣ ዜማና ቅኔን፣ ድጓና ጾመድጓን፣ ዝማሬና መዋሥዕትን፣ ከመጻሕፍትም ብሉይና ሐዲስን ልጆቻችን ደህና አድርገው እንዲማሩ፣ ለቤተክህነት መምህሮቻችን ለምን እርዳታ አይደረግላቸውም ? እየተባለ ትችቱ በሰፊው ቀረበ።

ደግነትና የዋህነት የሚያጠቃቸው ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ ምኒልክ፣ በሁለት ሐሳቦች ላይ ወደቁ። በአንድ በኩል ስለውጭ አገር ትምህርት አደገኛነት የተነገራቸው ሁሉ እውነት መስሎ ሲታያቸው፣ በሌላ በኩል ደግሞ ልጆ ወንድሜ የሚሏቸው አልጋ ወራሻቸው፣ የአገራችንን ሃይማኖትና ባህል የሚጐዳ ነገር ይሠራል ብለው ማመን አቃታቸው። በዚህ ጉዳይ ንግሥቲቱ አንድ አቋም



አንድ ሕፃን ተማሪ ፈተናውን አልፎ ከንጉሠ ነገሥቱ ሽልማት ሲቀበል፤



የነገዎቹን የኢትዮጵያ ፍሬዎች፤ ንጉሠ ነገሥቱ በየትምህርት ቤታቸው እየጐበኙ ሲንከባከቧቸው።

መውሰድ ተቸግረው ከፍ ያለ ጭንቅ ላይ መሆናቸውን ራስ ተፈሪ ሲሰሙ፣ የሚከተለውን ማስታወሻ አቀረቡላቸው።

« ..... ታላቁ ንጉሠ ነገሥታችን አባትዎ ዳግማዊ አፄ ምኒልክ፣ ኢትዮጵያን ወደ ሥልጣኔ ለመምራት መሠረት ነው ብለው ያመኑበትን የፈረንሣዊኛና የእንግሊዝኛ ትምህርት ለማስተማሪያ በስማቸው ባቋቋሙት ተማሪ ቤት፣ በመጀመሪያ እኛን የታላላቆቹን ልጆች ምሳሌ ሆነን እንድንማር ካደረጉ በኋላ፣ ትልቁ ምኞታቸው የኢትዮጵያ ልጆች ሁሉ ዘመናዊውን ዕውቀት እንዲገበዩበት ዕድል ለመስጠት እንደነበረ፣ እናቴ እመቤቴ ከማንም ይበልጥ የሚያውቁት ነው ብዬ አምናለሁ። እኔም ልጅዎ በመጀመሪያ የዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት የመማሪያው ክፍሎች እንዲስፋፉና ብዙ ተማሪዎች ለመቀበል እንዲቻል ያደረግኩት፣ ቀጥሎም ሕንፃውን በግል ገንዘቤ አሠርቼ ተፈሪ መኩንን የተሰኘውን አዲስ ተማሪ ቤት የከፈትኩት፣ የአባትዎን የታላቁ ንጉሠ ነገሥታችንን መሪ ሐሳብ ተከትዬ ነው። በዚህም መሠረት፦

1ኛ/ በዳግማዊ ምኒልክና አዲስ በተከፈተው በተፈሪ መኩንን ተማሪ ቤት፣ ለኢትዮጵያ ልጆች የሚሰጠው ትምህርት፣ የፈረንጆቹን የሥልጣኔ ጥበብ ለመቅሰም የሚያስፈልገውን ብቻ እንጂ፣ ስለውጭ አገር ሃይማኖትና ባህል ማስተማር በጥብቅ የተከለከለ መሆኑን፣

2ኛ/ የአባትዎን የታላቁ ንጉሠ ነገሥታችንን አርዓያ በመከተል፣ ቤተሰቦቻቸው እጅግ ችግረኞች ለሆኑት ተማሪዎች ትምህርታቸውን በትጋት ለመከታተል እንዲችሉ፣ የእርሳስና የወረቀቶች መግዣ የሚሆን መጠነኛ የገንዘብ እርዳታ ማድረጋችን፣ በድሀው ሕዝብ ዘንድ የሚያስመሰግነን እንጂ፣ የሚያስወቅሰን አለመሆኑን፣ የኢትዮጵያ ንግሥተ ነገሥታት እናቴ እመቤቴ እንዲያውቁልኝ ዝቅ ብዬ በታላቅ ትሕትና እለምናለሁ .... »

ከዚህ በላይ እንደታየው አልጋወራሽ ተፈሪ በላኩት ማስታወሻ፣ «.. የውጭ አገር ትምህርት እንዲስፋፋ ያደረግኩት፣ የአባትዎን የታላቁ ንጉሠ ነገሥታችንን መሪ ሐሳብ ተከትዬ ነው ... » ሲሉ የገለጹት፣ ንግሥቲቱን እጅግ ያስደሰተና የማረከ፣ ለተጨነቁበትም ጉዳይ የተረጋገጠ ዋስትና የሰጠ ስለሆነ፣ ዘውዲቱ ምኒልክ ከመሳፍንቱና ከመኳንንቱ፣ እንዲሁም ከቤተክህነት መሪዎች የቀረቡላቸውን ስሞታዎች፣ ምንም እንኳ ትክክል አይደለም ብለው ለመቆጣት ባይደፍሩም፣ በለሰለሰ አነጋገር አለመቀበላቸውን የሚገልጽ መልስ ሰጡ።

« .... ልጄ ወንድሜ አልጋወራሽ ተፈሪን ጠይቁው፣

አንደኛ/ በተማሪ ቤቶቹ ውስጥ ከእኛ ሃይማኖትና ባህል ውጭ፣ የፈረንጆቹን ጉዳይ ማስተማር ጨርሶ መከልከሉን፣

ሁለተኛ/ ለተማሪዎቹ ደሞዝ ተቆረጠላቸው የተባለው፣ ቤተሰቦቻቸው ችግረኞች ለሆኑባቸው ልጆች፣ የመማሪያ እርሳስና ወረቀቶች ለመግዣ የሚሰጥ እርዳታ እንጂ፣ እንደ መንግሥት ሠራተኛ የወር ደሞዝ የተመደበ አለመሆኑን አረጋግጠ ስለነገረኝ፣ እናንተም ይህንኑ እንድታውቁት ይሁን። .... » በማለት ንግሥተ ነገሥታት

ዘውዲቱ የሰጡት መልስ፣ የተቃዋሚዎቹን ሐሳብ ያከሸፈው ስለሆነ፣ ለራስ ተፈሪ ትልቅ ድል ሆነ።

-- ከዚህ በኋላ ነው ! ተፈሪ መኰንን አብዛኛውን የሥራ ጊዜያቸውን በትምህርት ጉዳይ ላይ በማዋል ብዙ ተማሪዎች ለማግኘት የቻሉት፣

-- ከዚህ በኋላ ነው ! ተፈሪ መኰንን ለወደፊቲቱ ኢትዮጵያ ኃላፊነትን ለመቀበል የሚችሉትን ወጣቶች፣ የመጀመሪያ ደረጃ ትምህርታቸውን አስጨርሰው ለከፍተኛው ትምህርት በብዛት ወደ ውጭ አገር ለመላክ የቻሉት፣

-- ከዚህ በኋላ ነው ! ተፈሪ መኰንን የችግረኞችን ቤተሰብ ልጆች እየረዱ በማስተማር የሕዝብ ወገን መሆናቸውን ስለአሳዩ፣ የመሳፍንትና የመኳንንት ዓድማ አያሠጋኝም ብለው በልበ ሙሉነት ለመሥራት የቻሉት፣

ጥቅምት 21 ቀን 1919 ዓ.ም ከዳግማዊ ምኒልክና ከተፈሪ መኰንን ተማሪ ቤቶች፣ በታሪክ ለመጀመሪያ ጊዜ ሠላሳ ሦስት /33/ ወጣቶችን ለከፍተኛ ትምህርት ወደ ውጭ አገር ለመላክ በመቻላቸው፣ ተፈሪ መኰንን በሕይወት ዘመናቸው ካጋጠማቸው ደስታ አንዱ እንደሆነ በሰፊው ሲነገር ሰምተናል። በአንድ ጊዜ እነዚህ ሠላሳ ሦስት ተማሪዎች ወደ ውጭ አገር ሲጓዙ፣ አልጋወራሹ ባሰናበቷቸው ዕለት፣ ከተማሪዎቹ ወኪልና ከራስ ተፈሪ የተገለጹት ስሜቶች፣ ምንጊዜም በታሪክ የሚታወሱ መሆን ይገባቸዋል።

ሞገስ ወልደዮሐንስ የተባለው ወጣት በጓደኞቹ ስም ሆኖ ባደረገው ንግግር፣ « .... **ዓለምን ያዳነ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ፣ ደቀመዛሙሮቹን የመረጠው ከታናናሾቹ ወገን እንጂ፣ ከታላላቆቹ አልነበረም። እነሆ አሁንም ልዑል ጌታችን ኢትዮጵያን ከጨለማ ወደ ብርሃን ለማሻገር የመረጧቸው አገልጋዮች፣ ከሕዝቡ መካከል ስለሆነ ፍሬያቸውን ለማየት እንዲያበቃዎ አምላካችንን እንለምነዋለን ...** » በማለት የገለጸው አስተያየት፣ በዘመኑ የአገራችን ሕዝብ የነበረውን አስተሳሰብ የሚያመለክት ሆኖ እናገኘዋለን። ራስ ተፈሪም በበኩላቸው ለኢትዮጵያ ሕይወትና ዕድገት፣ አንድነት ኃይል፣ መለያየት ጉዳት መሆኑን ካስረዱ በኋላ፣ « .... **እኔ ሰው ነኝ፣ ሟች ነኝ። ለማትሞተው አገራችን ረዳት እንድትሆንዋት እግዚአብሔርን እለምንላችኋለሁ** .... » ሲሉ የተናገሩት ልብ የሚነካ ቃል፣ የተማሪዎቹን መንፈስ በደስታና በሐዘን አሸብሮት ነበር። በዚያን ጊዜ፣ ወጣቱ ሞገስ ወልደዮሐንስ እንደተናገረው፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ኢትዮጵያን በንጉሠ ነገሥትነት በመሩበት ዘመን፣ በአርባ አራቱ ዓመታት ውስጥ፣ ከጠቅላይ ሚኒስትር ጀምሮ የካቢኔ ሚኒስትሮቻቸውን የመረጧቸው፣ ከመጀመሪያ ደረጃ ትምህርት አንሥቶ እስከ ዩኒቨርሲቲ ድረስ ካስተማሯቸው መካከል መሆኑን ወደፊት እናያለን።

# ምዕራፍ ፬

## የኢትዮጵያ ጠላት ሙሶሊኒ እንዴት ለዚህ ደረጃ በቃ ?

በጣልያን ሕዝብ ላይ ለሃያ ሁለት ዓመታት ወሰን የሌለው ሥልጣን ይዞ የነገሠው ፋሽስቱ ቤኒቶ ሙሶሊኒ፣ ኢትዮጵያን ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ እንዴት እንደ ወረራት፣ ዝርዝር ታሪኩን ከማቅረባችን በፊት፣ የዚህን ሰው ወደዚህ ዓለም አመጣጥና ቀጥሎም ከምን ተነሥቶ የአገሩ መሪ ለመሆን እንደበቃ፣ ማወቁ ጠቃሚ ይሆናል።

እ.ኤ.አ እሁድ ሐምሌ 29 ቀን 1883 ዓ.ም፣ በሰሜን ጣልያን በሮማኛ አውራጃ ቫራኖ ዴይ-ኮስታ በተባለችው ወረዳ ውስጥ፣ የብረታ ብረት ሠራተኛ ከሆነው ከሲኞር አሌሣንድሮ ሙሶሊኒ እና የመሠረተ ትምህርት አስተማሪ ከሆነችው ከሲኞራ ሮዛ ሙሶሊኒ፣ አንድ ወንድ ልጅ ተወለደ። ወዲያውም ወላጅ አባቱ ይህን የመጀመሪያ ልጁን ቤኒቶ-አምሊካር-አንድሬአ-ሙሶሊኒ፣ (Benito--Amlicar-Andrea Mussolini) ተብሎ እንዲሠየምለት በሚኖርበት ወረዳ ማዘጋጃ ቤት አስመዘገበ።

አሌሣንድሮ ሙሶሊኒ፣ ይህን "ቤኒቶ " የተባለውን የመጀመሪያ ስም ለልጁ ያወጣለት፣ በቀድሞው የሜክሲኮ ታሪክ ውስጥ የሬፑብሊክ አስተዳደር እንዲመሠረት፣ ከፍተኛ ተጋድሎ ያደረገውን " ቤኒቶ ዡዋሬስን" (Benito Juarez) በማሰብ ሲሆን ሌሎቹን አምሊካርና አንድሬአ የተባሉትን ሁለት ስሞች የቀጠለው፣ ራሱ አሌሣንድሮ ለሚያደንቃቸው ለሁለት የጣልያን ሶሲያሊስቶች መታሰቢያ ለመስጠት አስቦ ነው እየተባለ ይነገርለታል። አሌሣንድሮ ሙሶሊኒ፣ ከልጅነቱ ጀምሮ በጣልያን የሶሲያሊስት ፓርቲ በአባልነት የተመዘገበ ቢሆንም፣ በየመንደሩ እየዞረ በሚጭረው ጠብና በሚያካሂደው ረብሻ፣ ከሶሲያሊስትነቱ ይልቅ አናርኪስት የሆነው ጠባዩ ጉልቶ የሚታይበት ነበር። በተጨማሪም አንዳንድ የታሪክ ጸሐፊዎች እንደገለጹት፣ ሲኞር አሌሣንድሮ ስሙ የሚታወቀው፣ በየአደባባዩ እየዞረ መንግሥትን ለመቃወም ያለማቋረጥ በሚያሰማው ጩኸትና፣ በተጨማሪም በመጠጥ ኃይል እየተሸነፈ ሴቶች በማደንና በማጉላላት ነው ይባላል። በብረታ ብረት ቀጥቃጭነት ሞያው፣ ተግቶ በመሥራትና ገቢውን በማሻሻል ፋንታ፣ ጊዜውን የሚያባክነው በፖለቲካ ጉዳይ ስለሆነ፣ ሚስቱ ሲኞራ ሮዛ በአስተማሪነት ብዙ ደክማ የምታገኘው የወር ደሞዝ፣ የቤተሰቡን ኑሮ የሚያሟላላት አልነበረም። ከዚህም የገቢ እጥረት የተነሣ፣ በሙሶሊኒ ቤት በየዕለቱ ምሣና እራት የሚዘጋጀው ፓስታና የበቆሎ ዳቦ ብቻ ሲሆን፣ እንደ ልደትና የትንሣኤ በዓል ካልሆነ በስተቀር፣ ሥጋ የሚበሉበት ጊዜ እንደ ብርቅ የሚታይ ነበር።

የተወለደው ወንድ ልጅ ቤኒቶ ሙሶሊኒ፣ ከሕፃንነቱ ዘመን ጀምሮ እንደ አባቱ ጠባዩ እጅግ አስቸጋሪና እልኸኛ ስለነበረ፣ ዕድሜው ደርሶ ተማሪ ቤት ከገባም በኋላ፣ ከጓደኞቹ ጋር በሆነ ባልሆነው ጠብ የሚጭር ተደባዳቢና ቀማኛ ሆነ። እናቱ

ሲኞራ ሮዛ በካቶሊክ ሃይማኖት የጸናችና በሞያዋም አስተማሪ ስለሆነች፤ ልጇን ቤኒቶን ሳሌዚያኖ (Saleziano) በተባለ በካቶሊክ ቀሳውስቶች በሚካሄድ ትልቅ ትምህርት ቤት አስገብታ፤ ከአቅሟ በላይ ገንዘብ እየከፈለች በዲሲፕሊን እያደገ እንዲማርላት ብዙ ጥረት አደረገች። ነገር ግን በገንዘብ እጥረት ምክንያት ቤኒቶ በዚህ በታወቀ ኮሌጅ ትምህርቱን ለመቀጠል ከማይችልበት ደረጃ ደረሰ። ቤኒቶ ምንም እንኳ በጠባዩ እጅግ አስቸጋሪነቱ የታወቀ ቢሆንም፤ በቀለም ትምህርት ብልህነቱን አስተማሪዎቹ ስለመሰከሩለት፤ እናቱ ሲኞራ ሮዛ፤ ለልጇ የነፃ ትምህርት ዕድል እንዲሰጠው በማለት ችግሯን አሳዝና አመለከተች። ባቀረበችው ማመልከቻ ይፈቀድልኛል ብላ በተስፋ ስትጠባበቅ፤ ኮሌጁ ለቤኒቶ የነፃ ትምህርት መስጠት አይቻልም የሚል መልስ ሰጣት ። በዚህ እጅግ አዝና ከማልቀሷም በላይ፤ « ... ድህነቴ ዛሬ ገና ታወቀኝ .... » ብላ ምሬቷን ለአንዲት የጐረቤት ወዳጇ ገለጸችላት። በመሠረቱ፤ ኮሌጁ ለቤኒቶ የነጻ ትምህርት ዕድል ለመስጠት ፈቃደኛ ያልሆነው፤ በዚህ አስቸጋሪ ጠባዩ የተማሪዎቹን ሰላም መንሣቱን ይቀጥላል በሚል ፍራቻ እንጂ፤ ድሃ በመሆኑ አልነበረም። ቤኒቶ አንድ ቀን የኮሌጁ መምህር አበሳጭቶኛል ብሎ ቀይ ቀለም በጥብጦ እፊቱ ላይ እንደረጨበትና፤ አንዱን ጓደኛውን ደግሞ ሰድቦኸኛል ብሎ በሴንጢ እንደወጋው፤ በኮሌጁ የዲሲፕሊን ፋይል ተመዝግቦበታል። ስለዚህ፤ የኮሌጁ አስተዳዳሪዎች ልጁ ምንም ብልህ ቢሆን፤ ወደፊት ጠባዩ ይሻሻላል የሚል ተስፋ ማድረግ ስለአቃታቸው፤ እናቱ የጠየቀችለትን የነጻ ዕድል ሊሰጡት አልፈለጉም።

የቤኒቶ አባት ደግሞ፤ « ... ልጁ ወደፊት እንደ እኔው እንደ አባቱ የሕዝብ ታጋይ እንደሚሆን ስለታያቸው፤ የሳሌዚያኖ ኮሌጅ ቀሳውስቶች ትምህርቱን እንዳይቀጥል አገዱት ... » እያለ፤ በየመንደሩ መጠጥ ቤቶች ቢለፍፍም ምንም ዓይነት እርዳታ ለማግኘት አልቻለም። በመጨረሻው እናቱ ሲኞራ ሮዛ ባደረገችው ብርቱ ጥረት፤ ቤኒቶ ከሳሌዚያኖ ወጥቶ ወደ ሌላ አነስተኛ ወጭ ወደሚጠይቅ ኮሌጅ በመዛወር፤ ትምህርቱን እንዲቀጥል አደረገች። ሆኖም አስቸጋሪው ቤኒቶ፤ በዚህ በተዛወረበትም ኮሌጅ ማታ ማታ ጓደኞቹን እርስ በርሳቸው እያበጣበጠ ሰላም ስለነሣቸው፤ የኮሌጁ አስተዳዳሪዎች ከአዳሪነት ተወግዶ በተመላላሽነት ብቻ እንዲማር ፈረዱበት። ይህ ውሳኔ ለእናቱ ለሲኞራ ሮዛ ከባድ ችግር የሚፈጥር ነበር። በከተማው ውስጥ ለቤኒቶ አንዲት ክፍል ማደሪያ ለመከራየትና ለቀለቡም የሚያስፈልገው ገንዘብ፤ ለኮሌጁ በአዳሪነት ከምትከፍለው ወጭ የበለጠ ጨመረባት። ሲኞራ ሮዛ ልጇ አንድ ደረጃ ላይ እንዲደርስላት ስለፈለገች፤ ከጓደኞቿ እርዳታ እያገኘች፤ በዚህ ፎርሊምፖፖሊ (Forlimpopoli) በተባለው ኮሌጅ የመጀመሪያ ደረጃ ትምህርቱን ካከናወነ በኋላ፤ የሁለት ዓመት የመምህርነት ኮርስ ወስዶ ዲፕሎም ተቀበለ። የቤኒቶ የአስተማሪነት ዲፕሎም ማግኘት ለእናቱ ለሲኞራ ሮዛ ይህን ያህል የሚያረካ ውጤት አልነበረም። የእሷ ፍላጐት የሁለተኛ ደረጃ ትምህርቱን ጨርሶ ወደ ዩኒቨርሲቲ እንዲቀጥል ሲሆን፤ አባቱ ደግሞ ልጁ በዚህ በተመረቀበት የአስተማሪነት ዲፕሎም፤ ለመኖሪያው በቂ የሆነ የወር ደሞዝ ማግኘት እንደሚችልና የጣልያን ሶሲያሊስት ፓርቲ አባል ሆኖ አንድ ትልቅ ደረጃ ላይ እንደሚደርስ ሙሉ ተስፋ አሳደረ። ምን ይሆናል ? ቤኒቶ ይህን ለመጀመሪያ ደረጃ ትምህርት ቤት መምህርነት የሚያበቃውን ዲፕሎም ይዞ በየወረዳው ባሉት ተማሪ ቤቶች ሥራ ቢጠይቅ፤ በታወቀውና በሚነገርለት ጠባዩ ምክንያት የሚቀበለው አጣ። በተጨማሪም የአባቱ የአሌሣንድሮ ዝና የቤኒቶን ዕድል የሚዘጋ እንጂ የሚከፍት አልነበረም።

የአስተማሪነት ሥራ በማጣት ለአንድ ዓመት ያህል ከተንሳላ በኋላ፣ በዚያው በሚኖርበት በሮማኛ አውራጃ፣ ፕሬዳፒዮ (Predappio) በተባለው የወረዳ ማዘጋጃ ቤት የጸሐፊነት ክፍት ቦታ ስለነበረ፣ ቤኒቶ ከአመልካቾቹ ጋር ተወዳድሮ ፈተናውን በአንደኛነት አለፈ። ይሁን እንጂ፣ የቤኒቶ ዕድል አሁንም አላማረም። የማዘጋጃ ቤቱ ሹም፣ « ... **ምንም እንኳ ፈተናውን በሚገባ ያለፍክ ቢሆን፣ ጠባይህን ስለምናውቅ ልንቀበልህ አንችልም** ... » የሚል መልስ ሰጠው። ቤኒቶ እጅግ ተበሳጨ። አባቱም ከምሬቱ ብዛት ወደ ማዘጋጃ ቤቱ ሹም ቢሮ ሄዶ፣ « ... **እናንተ የሕዝብ ጨቋኞች፣ ይህን ዛሬ በሥልጣናችሁ ያጠቃችሁትን ልጄን አንድ ቀን ጌታዬ ብላችሁ ጫማውን የምትስሙበት ጊዜ ይደርሳል** ... » ብሎ ተሳደበ።

እንግዲህ ምን ይሻላል ? አባትና ልጅ ያለን ዕድል የሶሲያሊስት ፓርቲ ታጋዮች መሆን ብቻ ነው ብለው ወሰኑ። ቤኒቶ በእናቱ ብርታት ይከተለው የነበረውንም የካቶሊክ ሃይማኖት ማተቡን በጥሶ፣ « ... **ከእንግዲህ ወዲህ የእግዚአብሔርን መኖር አላምንም** ... » እያለ፣ በየአደባባዩ ዲስኩሩን ማስተጋባት ቀጠለ። በዚህ አኳኋን እናቱ ሲኖራ ሮዛ፣ የተመኘችው ሁሉ አልሆነላትም። ባላት አቅም ስትለፋ የኖረችው፣ ልጇ ጥሩ አስተዳደግና ትምህርት አግኝቶ እንደ አባቱ የፖለቲካ በጥባጭ እንዳይሆንባት ለማዳን ነበር። ቤኒቶ ምንም እናቱን ቢወዳት፣ በመንፈስም ሆነ በጠባይ አባቱ ስለሚማርከው፣ ምኞቷን አልተከተለላትም። አባቱ ሲኞር አሌሣንድሮም፣ የልጅ ጓደኛ በማግኘቱ እጅግ ከመደሰቱም በላይ፣ በስም ሶሲያሊስት፣ በተግባር አናርኪስት፣ የሆነ ትግሉን በይበልጥ ለማስፋፋት ትልቅ ተስፋ አሳደረ። በዚህ አኳኋን አባትና ልጅ ተያይዘው ከጠዋት እስከ ማታ መንግሥትን በመቃወምና በየፋብሪካው እየዞሩ የሠራተኞችን ዓድማ በመጉንጉን ሲለፉ ቢውሉም፣ ማታ ወደ ቤታቸው ሲመለሱ ለዳቦ መግዣ እንኳ የሚሆናቸውን ገንዘብ የሚሰጣቸው አልነበረም። ቤኒቶ ምንም እንኳ የተፈጥሮ ዝንባሌው በሆነው በፖለቲካ ትግል መንፈሱ ቢረካ፣ ጦም አዳሪነቱ እየሰለቸው ስለመጣ፣ ገንዘብ ለማግኘት አቋራጫውን ወደ መጥፎ ጉዳና ለወጠ። ጠዋት እየተነሣ ከአባቱ ጋር ወደ ሶሲያሊስት ፓርቲ ቢሮ በመሄድ ፋንታ፣ በየመንደሩ እየዞረ በእግራቸው ከሚንሸረሸሩት ሸማግሌዎችና አሮጊቶች ላይ ገንዘብ መቀማትና እየሮጠ ማምለጥ፣ ዓይነተኛ ሥራ አድርጐ ቀጠለበት። በሚያገኘውም ገንዘብ ሴቶችን በማደን፣ በየመጠጡ ቤት ከቢጤዎቹ ጉረምሶች ጋር በመደባደብና ከተማ በመበጥበጥ የታወቀ ሰው ሆነ። በየጊዜው በፖሊስ እየታደነ ቢታሰርም፣ ባለው ኃይለኛ በሆነው ተናጋሪ አንደበቱ፣ አሳሪዎቹን እየሰበከና እያታለለ በቶሎ ስለሚፈታ፣ የሮማኛ አውራጃ ነዋሪ ሕዝብ በወር ከሳምንት የበለጠ ሰላም የሚያገኝ አልሆነም። አባቱ አሌሣንድሮ ልጄ አንድ ቀን የጣልያን መሪ ይሆንልኛል ብሎ ሲመኝ፣ እናቱ ከፖለቲካ ጣጣ ይልቅ በትምህርቱ ገፍቶ አንድ ቁም ነገር ላይ እንዲደርስላት ስትፈልግ፣ ቤኒቶ ሁሉንም ትቶ ወደ ወሮበላ ሕይወት ተዛውሮ ሲጨፍርና አልሆን ቦታ ሲልከሰከስ፣ የውርዴ በሽታ ይዞት ሥቃይ ላይ ወደቀ። በእናቱ በሲኞራ ሮዛ ብርቱ ጥረት፣ ቤኒቶ ሕክምና አግኝቶ ከተሻለው በኋላ፣ በዚህ በጀመረው መንገድ ሕይወቱን መቀጠል እንደማይችል ስለተገነዘበ፣ አገሩን ለቅቆ ወደ ሌላ የሰው አገር መሰደድን መረጠ። የምትወደው እናቱም ሁኔታውን ደህና አድርጋ ስለተረዳችለት፣ ልጇ አጠገቤ ሆኖ በአሳፋሪ ሁኔታ ሞቶ ከምቀብረው፣ ወደ ሌላ አገር ተሰዶ ዕድሉን ቢሞክር ይሻላል ብላ የመሳፈሪያ ስንቅ ሰጥታ፣ እ.ኤ.አ በሰኔ ወር 1902 ዓ.ም ስዊስ አገር ስደተኛ ሆኖ እንዲገባ አደረገችው።

# ስደተኛው ቤኒቶ

በዚያን በ1900 ዓ.ም መጀመሪያ ላይ፤ በስዊስ አገር በግንበኝነትና በድንጋይ ጠራቢነት ሞያ የሚሠሩ፤ ቁጥራቸው በርከት ያለ የጣልያን ስደተኞች ስለሚኖሩ፤ ቤኒቶ ዤኔቭ እንደደረሰ፤ ወደ እነዚሁ ያገር ሰዎች ተጠግቶ ሠርቶ ለመኖር ወሰነ። በግንበኝነት ሞያ ከመሰልጠኑ በፊት፤ ድንጋይ በመፍለጥና በመጥረብ፤ አሸዋና ኖራ እያቦካ ለግንበኞቹ አቀባይ በመሆን ብዙ እየለፋ መኖር ጀመረ።

በስዊስ አገር ተሰደው ኑሮአቸውን ያቋቋሙት የጣልያን ባለሞያዎች፤ እጅግ አብዛኛዎቹ ምንም ዓይነት የቀለም ትምህርት የሌላቸው በመሆናቸው፤ ሐሳቡን በጽሑፍም ሆነ በቃል አፍታትቶ የሚገልጸውን ቤኒቶ ሙሶሊኒን እያደር ሲያጠኑት፤ በችሎታው ከፍ ያለ አክብሮት አደረባቸው። ቤኒቶም፤ የእነዚህን ሰዎች ደካማ ጐን ደህና አድርጐ ስለተረዳው፤ ማታ ማታ እየሰበሰበ የአራት መደብ ሒሳብ አሠራርና የቀለም ትምህርት በማስተማር ከማረካቸው በኋላ፤ ያችን ተንኮሉን ብቅ አድርጐ፤ ከመንግሥትና ከአሠሪዎች ጋር በመታገል የወዝ አደሩን ሕዝብ መብት ለማስከበር የሚቻልበትን መንገድ በማስረዳት መንፈሳቸውን ቀሰቀሰው። አንድ ዓመት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፤ በስዊስ አገር ለሚኖሩት የጣልያን ተወላጆች ግንበኞችና የልዩ ልዩ ሥራ ባለሞያዎች ማሕበር ተቋቁሞ፤ ቤኒቶ ሙሶሊኒ ዋና ጸሐፊያቸው ሆኖ ትግሉን እንዲመራላቸው፤ ሁሉም በአንድ ቃል መርጠው ኃላፊነቱን ሰጡት።

ቤኒቶ የአንድ እርምጃ ስፋት ያለው ሥልጣን ሲያገኝ፤ በአሥር ጊዜ አጥፍ አራዝሞ መጠቀም የተለየ ስጦታው ስለሆነ፤ እነዚህን የጣልያን ስደተኞች ሰብስቦ፤ አሠሪዎች በሠራተኞቹ ላይ የሚፈጽሙት ጭቆናና በደል ምን ያህል አሳዛኝ መሆኑንና የስዊስ መንግሥትም ለጥቅሙ ሲል ባለገንዘቦችን ምን ያህል እንደሚደግፋቸው ሲያስረዳቸው፤ ሁሉም በጋለ መንፈስና ደስታ አሜን ብለው ተቀበሉት። ይህንንም በወዝ አደሩ ሕዝብ ትከሻ ላይ የወደቀውን ጭቆና ለማላቀቅና ሠራተኛው ሕዝብ በሥራውና በድካሙ መጠን እንዲከፈለው ለማስደረግ፤ የሚዘጋጀውን ዓድማና የሚከናወነውንም ሰላማዊ ሠልፍ በሚገባ አስጠናቸው። እነዚህ የዋህ ሰዎች እንደተመከሩት፤ ለፖሊስና ለፀጥታው ክፍል ሳያስታውቁ፤ ቤኒቶ ሙሶሊኒ በወሰነላቸው ቀን ሥራቸውን አቁመው፤ " ተበደልን ! ግፍ ተፈጸመብን ! " እያሉ በመጮህ ተሰልፈው በከተማው አደባባይ ሲርመሰመሱ፤ የስዊስ ኮንፌዴራል መንግሥትና የዤኔቭ ካንቶን፤ ከዚህ ቀደም ያልደረሰ አዲስ ነገር በመሆኑ ደነገጡ። ወዲያውም ባለሥልጣኖቹ የሰልፈኞቹን ዋና ዋና ተቀዳሚዎች ወደ ቢሮአቸው አስገብተው፤ መብታችሁ እምን ላይ እንደ ተጓደለና ጭቆና እንደ ደረሰባችሁ ብታስረዱን፤ ችግራችሁን ሁሉ ለማሻሻል ዝግጁ ነን አሏቸው። ዓድመኞቹ ለተጠየቁት መልስ መስጠት ተሳናቸው። በመሠረቱ እነዚህ ሰዎች ተበድላችኋል ተብለው ስለተሰበኩ፤ ለዓድማው በሰልፍ መውጣታቸውን እንጂ፤ የተበደሉትን ለማስረዳትና የሚሻሻልላቸውን ለመጠየቅ አልተዘጋጁም ነበር። ተጨቁናችኋል ብሎ የቀሰቀሳቸውና ለሰልፉ ያዘጋጃቸው ቤኒቶ ሙሶሊኒ፤ በስዊስ አገር የመኖሪያውና የሥራ ፈቃዱ ስላልወጣለት፤ በዓድመኞቹ መካከል ተገኝቶ በሚያውቀው ጥበብ አስረጂ ለመሆን አልቻለም። በመጨረሻው እነዚህን ዓድመኞች መንግሥት በወግ ተቀብሎ ሲያነጋግራቸው፤ ችግራቸው ምን እንደሆነ ለማስረዳት ስላልቻሉ፤ ተሳስተናል በማለት ይቅርታ ጠይቀው ወደየቤታቸው ተመለሱ።

እነዚህ የጣልያን ተወላጆች፣ በስደት ከመጡበት ጊዜ ጀምሮ የስዊስን ሕግና ሥርዓት እየተከተሉ በሰላምና በደስታ እየሠሩ፣ በአገራቸው ከነበራቸው ኑሮ እጅግ የተሻለ ሕይወት አግኝተው በሰላም ሲኖሩ፣ ቤኒቶ መጥቶ በተንኮለኛው ጥበቡ ስለመረዛቸው፣ በማያውቁት ዓድማ ውስጥ ገብተው ጊዜያቸውን በከንቱ ሲያጠፉ ተገኙ። የገኔቭ አስተዳደርና የፀጥታው ክፍል ጉዳዩን ሲከታተሉ፣ በሰሜን ጣልያን ከነአባቱ አናርኪስት ሆኖ የሕዝቡን ሰላም በማደፍረስ የታወቀውና ከሁለት ዓመት ወዲህ በስደተኝነት ወደ ስዊስ የመጣው ቤኒቶ-አምሊካር-አንድሬአ-ሙሶሊኒ፣ የዚህ ዓድማ ቀንደኛ አዘጋጅ መሆኑን ደረሱበት። የጣልያኖቹም የግንበኞች ማህበር እዚህ ስሕተት ላይ የጣለን ቤኒቶ ሙሶሊኒ ስለሆነ፣ ከዛሬ ሚያዝያ 5 ቀን 1904 ዓ.ም ጀምሮ ከማህበራችን ዋና ጸሐፊነት ሽረነዋል ብለው መግለጫ ሲያወጡ፣ የገኔቭ ካንቶንም በማግስቱ ሚያዝያ 6 ቀን 1904 ዓ.ም ቤኒቶ ከስዊስ ተባርሮ ወደ አገሩ እንዲመለስ እስከ ጠረፉ አድርሰው አሰናበቱት።

## ገኔቭ ሰላም አገኘች
## ሮማኛ እንደገና አዘነች

ቤኒቶ ሙሶሊኒ ከስዊስ በመባረሩ፣ አንዳንድ ጋዜጦች ገኔቭ ሰላም አገኘች እያሉ የሕዝቡን ደስታ ሲያፋፍሙ፣ በሰሜን ጣልያን የሮማኛ ነዋሪዎች ደግሞ፣ ሰይጣኑ ተመልሶ መጣብን በማለት እጅግ አዘኑ።

ስደተኛው ወደ ትውልድ አገሩ ሲመለስ ቤተሰቦቹን በደህና አላገኛቸውም። እናቱ ሲኞራ ሮዛ በቱቤርኩሎዝ በሽታ አልጋ ይዛ ትማቅቃለች። አባቱም ሲኞር አሌሣንድሮ ያንኑ የተለመደ ሕገ ወጥ ሥራውን እየቀጠለ ስለአስቸገረ፣ መንግሥት አስፈርዶ ወህኒ ቤት አስገብቶታል። ደግነቱ፣ ቤኒቶ ከገኔቭ ሲወጣ እነዚያ ዓድማ ሲያስተምራቸው የነበሩት የጣልያን ተወላጆች፣ በመጨረሻው አዝነውለት ለስንቁ የሚሆነው የስዊስ ፍራንክ አዋጥተው ስለሰጡት፣ ይህ ገንዘብ ወደ ጣልያን ሊሬ ሲመነዘር ብዙ ስለሆነ፣ ለስድስት ወራት የቤቱን ቀለብ የሚችልለት ሆነ። በዚህ ጊዜ ውስጥ ቤኒቶ ሥራ ፈልጐ ማግኘት ስላልቻለ፣ ዕድሜው ልክ ሐያ አንድ ዓመት ሲሞላ፣ የጣልያን መንግሥት ሕግ በሚፈቅደው መሠረት ለተወሰነ ጊዜ የውትድርና አገልግሎት ግዳጄን እፈጽማለሁ ብሎ ተመዘገበ። "Military Service" ይህንንም የውትድርና አገልግሎት ለሁለት ዓመታት በሚያከናውንበት ጊዜ የመኖሪያውን ወጭና ልብሱን ከኪስ ገንዘብ ጋር የሚችለው መንግሥት ስለሆነ፣ የሚወደውን ዳቦና ፓስታ እንዲሁም ቢያንስ በሳምንት ሁለት ጊዜ ማለፊያ የሆነ የሥጋ ምግብ እያገኘ ሲኖር፣ መደሰቱን ባይገልጥ እንኳ የቅሬታ መንፈስ አላሳየም።

በ1906 የሚሊታሪ ሰርቪስ ግዳጁን ፈጽሞ ከወጣ በኋላ፣ የቤኒቶ ትልቁ ችግር አሁንም ሥራ ማጣት ነበር። ለሁለት ዓመታት ከሮማኛ አውራጃ ተሰውሮ በስደት ቢኖርም፣ ያለፈ ታሪኩን የረሳለትና እንደ አዲስ ሰው የሚመለከተው አላገኘም። በማናቸውም የሥራ መስክ ዕድል እንዳያገኝ በሩ ተዘግቶበታል። ከዕለት ወደ ዕለት ችግሩ እየበረከተ በመጉላላቱ፣ እንደገና አገሩን ለቅቆ ወደ ደቡብ ፈረንሣይ በመሻገር፣ ማርሰይ በተባለው የወደብ ከተማ ሄዶ በስደተኝነት ለመኖር ፈቃድ ጠየቀ። የፈረንሣይ ባለሥልጣኖች ማመልከቻውን አጥንተው ውሳኔ ከማድረጋቸው በፊት፣ ችኩሉ ቤኒቶ፣ በገኔቭ እንዳደረገው ሁሉ፣ የጣልያን

ከሙኒቴዎች ወደሚኖሩበት ሰፈር ሄዶ፣ በሰላም እየሠሩ የሚኖሩትን ልዩ ልዩ የተግባረ ዕድ ባለሞያዎቹን እየሰበሰበ፣ ስለ ፖለቲካ ትግልና ስለ ዓድማ ዝግጅት ማስተማር ጀመረ። የፈረንሣይ የፀጥታ ፖሊሶች፣ እንደ ስዊሶቹ ችላ ብለው ጊዜ አልሰጡትም። ለሁለተኛ ጊዜ ሰፊውን ስብሰባ ለማካሄድ ከሚዘጋጅበት ቦታ በድንገት ደርሰው ከያዙት በኋላ፣ ቤኒቶ ሙሶሊኒ የመኖሪያ ፈቃድ ሳያገኝ ጠረፍ ዘሎ የመጣ ሥራ ፈት ነው በማለት፣ ውሎ ሳያድር ወደ አገሩ መለሱት።

ቤኒቶ ከፈረንሣይ አገር ተባርሮ ሲመለስ፣ ሕይወቱ ከምን ጊዜውም የበለጠ ጨለመበት። የምትወደውና የምትረዳው እናቱ ሲኞራ ሮዛ በቱቤርኩሎዝ ሕመም ተሰቃይታ ሞታለች። አባቱ ሲኞር አሌሣንድሮም ሕገ ወጥ በመባል በየጊዜው ስለሚታሰርና በሞያው አዘውትሮ ለመሥራት ባለመቻሉ ገቢው ስለአጠረበት፣ ኑሮው ሥቃይ ሆኖበታል። ራሱ ቤኒቶም ወደፊት ምን ሠርቶ መኖር እንደሚችል እጅግ ጨንቆታል። ከእነዚህም ተደራርበው ከመጡበት ችግሮች ለመላቀቅ የሚችል መስሎ ስላልታየው፣ በገዛ እጁ ሕይወቱን ለማጥፋት እንደሚያስብ አባቱ ተከታትሎ ደረሰበት። ሲኞር አሌሣንድሮ፣ ዘወትር የሚያስበውና የሚመኘው፣ የሶሲያሊስት ፓርቲ በምርጫ ድል አድርጉ ፓርላማውን በሚይዝበት ጊዜ፣ ልጁ ጠቅላይ ሚኒስትር ሆኖ ጣልያንን ለመምራት ይበቃል በማለት ስለሆነ፣ ቤኒቶ ይህ እምነት አድሮበት ትግሉን እንዲቀጥል ብዙ ጥረት አደረገ። « ... ራስን ገድሎ ከዚህ ዓለም መገላገል፣ መጀመሪያ ደመኛን ገድሎ ነው እንጂ፣ ለደመኛ ቦታ በመልቀቅ አይደለም ... » በማለት በየዕለቱ በሚሰጠው ምክር፣ ቤኒቶ ቀስ በቀስ መንፈሱን እያጠናከረ ሲሄድ አንድ ቀን የመልካም ዕድል በር ተከፈተለት።

## ከጦም አዳሪነት ወደ ጋዜጠኝነት

በመጋቢት 1908 ዓ.ም፣ የታወቀው የኮሙኒዝም ፈላስፋ ካርል ማርክስ (KARL MARX) የሞተበት የሐያ አምስተኛው ዓመት በሚከበርበት ዕለት፣ ቤኒቶ ሙሶሊኒ በጋዜጣ ላይ የጻፈው አርቲክል፣ በሶሲያሊስቶችና የግራ ክንፍ በሆኑ የፖለቲካ ፓርቲዎች ዘንድ፣ ከፍተኛ አድናቆትን አተረፈ። ቤኒቶ በጻፈው አርቲክል የገለጸው ሐሳብ ባጭሩ፣ « ... በምንኖርበት ዓለም ያጋጠሙንን የነፃነትና የመብት ችግሮች፣ እያንዳንዳቸውን እየለየን በማጥናትና ለእያንዳንዳቸውም በየመልካቸው መፍትሔ ለመስጠት በመሞከር አንዘልቀውም። ... ለችግሮቻችን ሁሉ ትልቁ ፍቱን መድኃኒት፣ የዚህን ዓለም ወደ ኋላ ጉታች የሆነውን ሥርዓት ገለባብጠን፣ በአዲስ አስተሳሰብ በመገንባት ብቻ ነው ... » የሚል ነበር። ቤኒቶ ይህ የጻፈው አርቲክል ብዙዎቹን የሶሲያሊስት ፓርቲ አባሎች በማስደሰቱ፣ የኑሮ መደገፊያ ገንዘብ እየተከፈለው ወደፊትም በዚሁ አኳኋን አስተሳሰቡን እየፈለቀቀና እያስፋፋ እንዲጽፍ አደራ ተሰጠው።

ቤኒቶ ይህን ዕድል እንዳገኘ፣ ወዲያውኑ የጋዜጠኝነትን ሞያ እየተመረኮዘ ከሥፍራ ወደ ሥፍራ በመዘዋወር በጣሊያን አገር የሶሲያሊስት ሬቮሉሽን ለማካሄድ ቆርጦ ተነሣ። በዚህ አቋሙ፣ አንድ ጊዜ ለባላገሩ ሕዝብ ተቆርቋሪ በመሆን የሊበራሉን መንግሥት እያወገዘ ሲጽፍ፣ ሌላ ጊዜ ደግሞ የሠራተኛውን መብት ለማስከበር ኢንዱስትሪያሊስቶቹንና ከበርቴዎችን በመዓረር የዓድማ ዝግጅት ሲያስተምር፣ ያለማቋረጥ ሌት ተቀን መሥራቱን ቀጠለ። የፀጥታው ፖሊሶችም ቤኒቶ የሚሠራው ሁሉ እንደ አባቱ ከሕግ ውጪ የሆነ የአናርኪስትነት ተግባር

ነው በማለት፣ በየጊዜው እየተከታተሉ እሥር ቤት መክተታቸውን አላቋረጡም ነበር። ደጋፊዎቹም ሶሲያሊስቶች፣ ምንም እንኳ የቤኒቶ የአናርኪነት ጠባይ የማይካድ ቢሆንም፣ በብዙ ረገድ የሚጽፈውና የሚገልጠው ሐሳብ የፓርቲውን ዕምነት የሚያዳብር ሆኖ ስለአገኙት፣ በታሰረ ቁጥር እየተሟገቱ ማስፈታቱንና ለመኖሪያው የሚያስፈልገውንም ወጭ ከመስጠት ችላ አላሉም። ቤኒቶ ግን ለሕግ መታዘዝን አልፈለገም። መንግሥትን መቃወም መብቱ ቢሆንም፣ በየጊዜው ሕገ ወጥ የሆነ እርምጃ ሲወስድ በተገኘ ቁጥር፣ ፖሊስ እየያዘ ሲያስረው፣ እሱም የእስር ቤቱን ሕይወት እየተላመደው፣ እንደ ፕሮፌሽናል ሥራ አድርጐ ሳይመለከተው አልቀረም። በሚታሰርም ጊዜ፣ በየሳምንቱ ለፓርቲው ጋዜጣ እየጻፈ የሚያቀርበውን አርቲክል ባለማቋረጡ፣ በየወሩ ሶሲያሊስቶቹ የሚሰጡት የኑሮ መደገፊያ ገንዘብ እንኳንስ ለራሱ አባቱንም ለመርዳት የሚያስችለው ሆነ።

የቤኒቶ አባት አሌሣንድሮም፣ ሚስቱ ከሞተች በኋላ፣ ሲኞራ ሐና ሉምባርዲ የተባለችዋን እሷም እንዲሁ ባሏ የሞተባትን ሴት አግብቶ፣ ዓመሉንም አሻሽሎ መኖር ጀመረ። ይህች የቤኒቶ እንጀራ እናት የሆነችው ሴት፣ ከሞተው ባለቤቷ ከወለደቻቸው አምስት ሴቶች ልጆች መካከል አራቱ ትዳር ሲይዙ፣ የመጨረሻዋ ራሄል ከእንጀራ አባቷ ከአሌሣንድሮ እና ከወላጅ እናቷ ከሲኞራ ሐና ጋር አብራ ትኖር ነበር። ቤኒቶ በየጊዜው ከእሥር ቤት በተፈታ ቁጥር፣ ወይም ደግሞ እንደገና ከመያዙ በፊት፣ አንዳንድ ጊዜ በሳምንት መጨረሻ ላይ እየመጣ አባቱና እንጀራ እናቱ ዘንድ ሲያርፍ፣ በዚች በምታምር የአሥራ ስድስት ዓመት ልጅ በሆነችው በራሄል ላይ የፍቅር ዓይኑን ጣለባት። ወዲያውም አሁን ማግባት አለብኝ ብሎ ተነሣ። አባት አሌሣንድሮ እና ሚስቱ አጥብቀው ተቃወሙ። ቤኒቶ ምክንያታችሁ ምንድን ነው? ብሎ ሲጠይቅ፣ አጥጋቢ መልስ ሊሰጡት አልቻሉም። እንዲሁ በደፈናው ራሄል በጣም ልጅ ስለሆነችና በመካከላችሁ ብዙ የዕድሜ ልዩነት ስላለ፣ (ቢያንስ አሥር ዓመት) ሌላ ጥቂት የበሰለችና ሥራም እየሠራች የምትረዳህ ቆንጆ ሴት ተመርጣ እንዳርህ ! የሚል ሐሳብ አቀረቡለት። ቤኒቶ ብው አለ። በእኔ ምርጫ እናንተን ምን አገባችሁ ? ሠርግ መደገስ በዓል ማዘጋጀት አያስፈልግም። በዛሬው ዕለት ከራሄል ጋር ጋብቻዬን ፈጽሚያለሁ ብሎ፣ በሠፈሩ ባለው ማዘጋጃ ቤት ሄዶ አስመዘገበ። በዚህ ጊዜ የሙሶሊኒን ቤተሰብ ምሥጢር እናውቃለን የሚሉ ጐረቤቶች ሁሉ ራሳቸውን ይዘው ኡ ኡ አሉ።

የቤኒቶ አባት ሲኞር አሌሣንድሮ እና የራሄል እናት ሲኞራ ሐና የምሥጢር ግንኙነት የጀመሩት የቤኒቶ እናት እና የራሄል አባት ከመሞታቸው በፊት ነው። ራሄል የተፀነሰችው ከአሌሣንድሮ ነው። ስለዚህ ራሄል የቤኒቶ ግማሽ እህት እንጂ የአባቱ የእንጀራ ልጅ አይደለችም። ይህንንም ሲኞራ ሐና መጽሐፍ ቅዱስ ተይዞ ብትጠየቅ፣ ሐሰት ነው ብላ አትምልም በማለት፣ ምሥጢር አዋቂዎቹ እምነታቸውን አጠነከሩ። ሆኖም ወሬው አደባባይ ወጥቶ የተገለጠ እንደሆነ፣ ቤኒቶ በጥይት ይጨርሰናል ብለው ሁሉም ስለፈሩ፣ አንገታቸውን አቀርቅረው ዝም አሉ። በዚህ አኳኋን ታሪኩን አተኩሮ ለሚመለከተው፣ ቤኒቶ የአባቱ የእንጀራ ልጅ ነች የተባለችውን ራሄልን ላግባ ብሎ ሲነሣ፣ ሲኞር አሌሣንድሮና ሲኞራ ሐና እንደዚያ ለምን ተቃወሙ ? የሚል ጥያቄ ያስቀርባል። በየትኛውም ዓለም የአንድን ቤተሰብ የሕይወት ምሥጢር ለማወቅ ከጐረቤት የቀረበ የለም። ምንም እንኳ ብዙ ጊዜ ከጐረቤት የሚሠራጨው ወሬ እየተጨማመረበትና እየተፋፋመ ነው ቢባልም፣ ፍንጭ ሳይኖረው ብቻውን የተፈጠረ አይደለም። በዚህም ዓይነት የቤኒቶ አባትና

የራሄል እናት ጋብቻውን አጥብቀው የተቃወሙት፣ እነሱ በግላቸው የሚያውቁት ጉድ ቢኖር ነው ለማለት ይቻላል።

የፈረደባት ራሄል፣ ይህን አስቸጋሪ ሰው ለማግባት ፈቃደኛ ነሽ ? ወይስ አይደለሽም ? ተብላ አልተጠየቀችም። ይልቁንም በምትማርበት ሠፈር ያወቀችውን፣ እሷም ትወደው እሱም ያፈቅራት የነበረውን የተማሪ ወጣት ሁለተኛ እንዳታየው፣ ድንገት ከመንገድ ላይ ቢያጋጥማት እንኳ ሰላምታ እንድትነፍገው ታዘዘች። ከዚህም ጊዜ ጀምሮ አባ ሰይጣን ቤኒቶን ተከትላ፣ እሱ በሚፈልገውና እሱ በሚያስበው መንገድ ብቻ ትዳሯን እንድታከብር ስለተፈረደባት፣ ምንም ዓይነት ምርጫ የሌለውን ሕይወት እስከ ዕድሜ ልኳ ቀጠለች።

## ቤኒቶ፣ የሶሲያሊስቶች አፈ ጉባኤ

ቤኒቶ፣ ይህችን (ግማሽ እህቱ) የአባቱ ልጅ ነች የተባለችዋን ራሄልን ባገባ በስድስተኛው ወር፣ አባቱ ሲኞር አሌሣንድሮ በድንገተኛ ሕመም በመሞቱ፣ እጅግ አዝኖ የወደፊት ዕድሉም የጨለመ መስሎ ታይቶት ነበር። ቀደም ሲል በታሪኩ እንደታየው፣ አባትና ልጅ አሌሣንድሮና ቤኒቶ በሚያደርጉት ትግል የሚስማሙ ብቻ ሳይሆኑ፣ በብዙ ረገድ እጅግ የሚመሳሰሉም ነበሩ። ሞት ከለያያቸው በኋላ፣ ቤኒቶ በብቸኝነት ተኮራምቶ በትካዜ በሚኖርበት ሰዓት፣ እ.ኤ.አ ታህሣሥ 1 ቀን 1912 ዓ.ም አንድ ያልጠበቀው ቴሌግራም ደረሰው። ይኸውም፣ « ... የጣልያን ሶሲያሊስት ፓርቲ አፈጉባኤ ለሆነውና እጅግ ለታወቀው አቫንቲ (AVANTI) ለተባለው ጋዜጣ፣ ቤኒቶ-አምሊካር-አንድሬአ-ሙሶሊኒ ዋና አዘጋጅ ሆኖ ተመርጧል። .... » የሚል ነው። በዚህ ቀን ለቤኒቶ ከዚህ የበለጠ የሚያስደስት ነገር ስለሌለ፣ በሚላኖ ከተማ ዘወትር ሕዝብ በሚሰበሰብበት አደባባይ ላይ ወጥቶ፣ እስክስታ እየወረደና እየጨፈረ የተለየ ትርዒት ሲያሳይ አመሸ። ዲክታተር ከሆነው መሠረታዊ ጠባዩ ጋር፣ በአንድ ጊዜ ይህን የመሰለ ትልቅ ሥልጣን ሲያገኝ፣ ከብዙ ዓመታት ጀምሮ አገሪቱን ሲመራ የኖረውን የነ ጂዮሊቲን (GIOLITTI) ሊበራል ፓርቲ መንግሥት አስወግዶ፣ በሶሲያሊስቶቹ ለመተካት እስችላለሁ ብሎ፣ ቤኒቶ ከመጠን በላይ ፈነደቀ።

ጥር 1 ቀን 1913 ዓ.ም የፈረንጆቹ የዘመን መለወጫ በዓል ከመከበሩ በፊት፣ ቤኒቶ ሙሶሊኒ አዲሱ ሥራውን ሲጀምር፣ ይህ አቫንቲ የተባለው የሶሲያሊስቶች ጋዜጣ፣ የሕዝብ ተቆርቋሪና መብት አስከባሪ በመሆን፣ የቀኙ መንግሥት ወድቆ ሶሲያሊስቶቹ በሕዝቡ ተመርጠው ሥልጣኑን እንዲረከቡ ለማድረግ የቀረጠበት ጽኑ ዓላማው መሆኑን፣ በብዕሩ በጻፈው በመጀመሪያው ርዕሰ አንቀጹ ላይ አብራርቶ አስረዳ። የቤኒቶ አጻጻፍና አቀራረብ የሕዝቡን መንፈስ የሚቀሰቅስና የሚማርክ በመሆኑ፣ ቀድሞ በሳምንት ሐያ ሺህ (20.000) ይታተም የነበረው ጋዜጣ፣ በጥቂት ወራት ውስጥ መቶ ሺህ (1000.000) አንባቢዎችን ሰበሰበ። በዚህ አካሄዱ እጅግ ቢበዛ በሚቀጥሉት ሁለት ዓመታት ውስጥ፣ በሊበራሎችና በሞደሬቶች ትብብር የሚመራውን የነጂዮሊቲን መንግሥት ጥሎ ሶሲያሊስቶቹን ለሥልጣን ያበቃቸዋል እያሉ፣ አብዛኛዎቹ የፖለቲካ ታዛቢዎች አስተያየታቸውን መስጠት ጀመሩ። ጥቂቶቹ ግን፣ ሙሶሊኒ ለአንድ ዓላማና ለአንድ ግብ ፀንቶ የሚቆም ሰው ስላልሆነ፣ በድንገት ከሶሲያሊስቶቹ ጋር ተቃቅሮ ከቀኞቹ ሊበራሎች ጋር ተሰልፎ ቢገኝ አይደንቀንም እያሉ ትንቢት ይሰነዝሩ ነበር። በመሠረቱ ቤኒቶ ሙሶሊኒ ሶሲያሊስት አልነበረም። ስዊስ አገር በተሰደደበት ጊዜ፣

ቭላዲሚር ሌኒን (VLADIMIR LENINE) እዚያው ነዋሪ ስለሆነ፤ በየጊዜው እየተገናኘን ስለ ዓለም ሬቮሉሽን አካሄድ እንወያይ ነበር እያለ፤ የሚነዛው ፕሮፓጋንዳ ሁሉ ውሸት መሆኑ ኋላ ተደርሶበታል። ቤኒቶ ስዊስ አገር የኖረው የጣልያን ተወላጆች ከሆኑት ግንበኞች ጋር እንጂ፤ ከታወቁት የግራ ክንፍ ኢንተሌክቱዋሎች ጋር አልነበረም። ከዚህም በላይ የማርክስንም ሆነ የሌኒንን ቴዎሪዎች በጥልቀት አጥንቶ የተረዳ አይደለም። አባቱ አሌሣንድሮም ልጁን ኮትኩቶ ያሳደገው፤ ሶሲያሊስትነትን በማስተማር ሳይሆን፤ ያለውን የነ ክሪስፒን መንግሥት በመቃወምና ድል በማድረግ፤ አንድ ቀን በሶሲያሊስቶች ስም የጣልያን መሪ ለመሆን እንዲበቃ ሞራሉን በማዳበር ነበር። ቤኒቶም በድፍረት መንግሥትን በመቃወም ያደረጋቸው ትግሎች ሁሉ፤ አናርኪስቶች የሚጠቀሙበትን መንገድ በመከተል እንጂ፤ የሶሲያሊስቶቹን ቴዎሪ በማብራራት ወይም በማስረዳት አልነበረም። በብዙ ረገድ፤ ለሕዝብ መብት ተቆርቋሪና ተጨናቂ ለመሆን ያደረገው ጥረት ሁሉ፤ ለራሱ የሥልጣን ፍላጐት ቅድሚያ በመስጠት መሆኑን ለመረዳት አያስቸግርም። በዚህ አኳኋን፤ ዛሬ የሶሲያሊስት ፓርቲ የኛ ታጋይ ነው ብሎ ለትልቁ የፕሮፓጋንዳ መሣሪያ ለሆነው ለአቫንቲ ጋዜጣ መሪ እንዳደረገው ሁሉ፤ የሊበራሉም መንግሥት ብልጥ ሆኖ የአንድ ትልቅ ኃላፊነት ቦታ ልስጥህ ቢለው፤ ቤኒቶ ወዲያውኑ የሶሲያሊስትነቱን ሸሚዝ አውልቆ ለመጣል እንደማያመነታ፤ አንዳንድ ሰዎች ይጠረጥሩት ነበር።

እ.ኤ.አ በ1914 ዓ.ም የመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ሲፈነዳ፤ የሶሲያሊስቶቹ አቋም ጣልያን ከዕብዶቹ ከጀርመንና ከኦስትሪያ-ሀንጋሪ፤ ወይም ከካፒታሊስቶቹ ከእንግሊዝና ከፈረንሣይ አንዱን ወገን ለይታ መካፈል የለባትም የሚል ስለሆነ፤ የአቫንቲ ጋዜጣ ዋና አዘጋጅ ሲኞር ሙሶሊኒ በዚህ ዓላማ ትግሉን ለማካሄድ ዝግጁ ሆነ። « ... ጣልያን የራሷ የሆነ የኑሮና የአስዳደር ችግሮች ስላሏት፤ ዛሬ ጥጋብ በዝቶባቸው ጦርነት ከከፈቱት አገሮች ጋር ምንም ጉዳይ የላትም ... » በሚል ሐሳብ፤ ሙሶሊኒ እያከታተለ የጻፋቸው አርቲክሎች፤ የወታደሩንም ሆነ የሕዝቡን መንፈስ የሚማርኩ ሆኑ። መቶ ሺህ ይታተም የነበረውም ጋዜጣ ተፈላጊነቱ እጅግ ስለበዛ፤ በዚያኑ ሰሞን እጥፍ ሆነ። የጣልያን ሶሲያሊስት ፓርቲ መሪዎችም፤ በዚህ የዓለም ጦርነት ጣልያን መካፈል የለባትም ሲሉ የወሰዱትን አቋም ሕዝቡ እንዲደግፋቸው፤ ሙሶሊኒ ከሚጠብቁት በላይ ባስገኘላቸው ከፍተኛ ውጤት ትልቅ ደስታ ስለተሰማቸው፤ የቤኒቶን የግል ሕይወት ለማሻሻል በሚላኖ ከተማ አንድ መኖሪያ ቤት እንዲገዛለት ገንዘብ ማሰባሰብ ጀመሩ። የእንግሊዝና የፈረንሣይ መንግሥታት ደግሞ፤ ጣልያን በጦርነቱ አብራቸው እንድትሰለፍ አጥብቀው ስለሚፈልጉ፤ የሙሶሊኒን የሶሲያሊስት ፕሮፓጋንዳ ቀልብሶ፤ የሕዝቡን ድጋፍ ለማግኘት ምን ማድረግ እንደሚሻል ለመተባበር ጠየቁ። የጣልያን መንግሥት መሪዎችም በጉዳዩ ላይ የተለየ ጥናት ካደረጉ በኋላ፤

1ኛ/ ይህ የመጀመሪያው የዓለም ጦርነት በእንግሊዝና በፈረንሣይ መንግሥታት ድል አድራጊነት ሲፈጸም፤ በቀድሞው ዘመን የኦስትሪያ ሀንጋሪያ ኢምፔሪያሊስቶች፤ በጉልበታቸው ከጣልያን የቀሙትን የሰሜን አውራጃዎች በሙሉ ለባለቤቱ እንዲመልሱ ቃል ከተሰጠ ፤

2ኛ/ ጀርመን ድል ሲሆን በአፍሪካ የያዛቸውን የኮሎኒ ግዛቶች፤ ጣልያን ከፈረንሣይና ከእንግሊዝ መንግሥታት ጋር እኩል የመካፈል ዕድል እንደሚኖራት ከተረጋገጠ ፤

ጣልያን ከዴሞክራሲ አገሮች ጋር ተሰልፋ፤ ኢምፔሪያሊስቶቹን አስትሪያ-ሀንጋሪያንንና ጀርመንን ለመውጋት ትችላለች ሲል፤ የሮማ መንግሥት በይፋ አስታወቀ፡፡ የእንግሊዝና የፈረንሣይ መንግሥታትም ሌላ ምርጫ ስለሌላቸው፤ ሁለቱንም ጥያቄዎች ተቀብለው ለማስፈጸም ቃል ገቡ፡፡

በዚህ ጊዜ፤ የሮማ መንግሥት ጥሩ የፐሮፓጋንዳ ዝግጅት አድርጐ፤ ጣልያን የጦርነቱ ተካፋይ ከሆነች በመጨረሻው የሚያስገኝላት ጥቅም ምን ያህል ከፍተኛ መሆኑን በማፋፋም፤ በሶሲያሊስቶቹ ሐሳብ የተመረዘውን የሕዝብ አስተያየት ለመቀልበስ ጥረቱን ሲቀጥል፤ በሚላኖ ከተማ ያልተጠበቀ አንድ ትልቅ ቦንብ ፈነዳ፡፡ የሶሲያሊስቶቹ አፈ ጉባኤ ሲኞር ቤኒቶ ሙሶሊኒ፤ በድንገት ኮቱን ገልብጦ « ... ጣልያን ከዓለም ታላላቅ ጉዳዮች ተለይታ ብቻዋን መቆም ስለማትችል፤ ከፈረንሣይና ከእንግሊዝ መንግሥታት ጋር እነዚህን ፊዎዳሎችና ኢምፔሪያሊስቶችን መውጋት ይገባታል ... » የሚል ለፊ ርዕስ አንቀጽ በመጻፍ በአቫንቲ ጋዜጣ ላይ ሰባት መቶ ሺህ ኮፒ አሳትሞ በተነ፡፡ በዚህ ከአቫንቲ ጋዜጣ ዋና መሪ በተገለጸው አስተያየት፤ የሊበራሎቹ መንግሥት ከሰማይ በወረደለት ትልቅ ደስታ ሲፍለቀለቅ፤ በሙሶሊኒ ላይ ፍጹም ዕምነታቸውን ያሳደሩት ሶሲያሊስቶቹ፤ በድንጋጤ ማዕበል ተውጠው የሚይዙትንና የሚጨብጡትን አጡ፡፡ ሙሶሊኒ ይህን እርምጃ የወሰደው በምን ምክንያት ይሆን ? እያሉ ሲመራመሩ፤ የአቫንቲ ጋዜጣ ዋና አዘጋጅ፤ ሶሲያሊስቶቹን ጠምዝዞ የጦርነቱ ደጋፊዎች እንዲያደርጋቸው፤ በፈረንሣዮችና በእንግሊዞች በገንዘብ ተደልሎ ነው የሚል መረጃ ደረሳቸው፡፡ የጣልያን ሶሲያሊስቶች ይህ ወሬ እውነት መስሎ ስለታያቸው፤ ጊዜ መውሰድ አልፈለጉም፡፡ በአስቸኳይ ጠቅላላ ስብሰባ አድርገው፤ ቤኒቶ ሙሶሊኒ ከአቫንቲ ጋዜጣ ዋና አዘጋጅነት እንዲሻርና፤ ከሶሲያሊስትም ፓርቲ አባልነት በፍጹም እንዲወገድ ውሳኔ ሰጡ፡፡

## አዲዮ ሶሲያሊዝም

ሶሲያሊስት ሬቮሉሽነር ነኝ በማለት፤ ለአሥራ አራት ዓመታት ሲታገልና ሲታሰር፤ ሲሰደድና ሲሰቃይ ከኖረ በኋላ፤ ቤኒቶ ሙሶሊኒ በድንገት ተነሥቶ "አዲዮ ሶሻሊዝም " ብሎ፤ በሕዝብ ዘንድ የታወቀበትን የታጋይ ሸሚዝ አውልቆ ሲጥል፤ ያልደነገጠ፤ ያልተገረመና ያላዘነ አልነበረም፡፡ ወዲያውም ትናንት ሲያጠቃቸው ከነበሩት ከሊበራሎቹና ከናሽናሊስቶቹ ፓርቲዎች ጋር በመስማማት "IL - POPOLO" የተሰኘ፤ አዲስ ጋዜጣ አቋቁሞ ወንድሞቹ የነበሩትን ሶሲያሊስቶች እንደዚያ ሲቃወማቸውና ሲያወግዛቸው፤ ምንም ዓይነት የሕሊና ፀፀት አላደረበትም፡፡፡ በዚህ አዲስ ባቋቋመው ጋዜጣ በመጀመሪያው ርዕስ አንቀጽ ላይ በገለጸው አስተያየት፤ « ... ትናንት የተናገርኩት፤ በትናንትናው ዕለት የነበረውን ጥቅማችንን አይቼ ነው፡፡ ዛሬ ደግሞ ለአገሬ ከትናንቱ የተለየና የተሻለ ዕድል ሲከፈትላት፤ የወደፊቱን መከተል እንጂ፤ የትናንቱን ስለተውኩት የሚያስደንቅ ነገር አይታየኝም፡፡ የጣልያን ሕዝብ የሚያስበው ለወደፊት፤ የሚጓዘው ወደፊት ነው እንጂ፤ በትናንቱ ላይ ጊዜውን ማጥፋት የለበትም ... » ሲል የጻፈውን፤ ሕዝቡ የተቀበለለት እጅግ በጋለ የደስታ መንፈስ ነው፡፡ ጣልያን ከፈረንሣይና ከእንግሊዝ ጋር ተሰልፋ፤ ኢምፔሪያሊስቶቹን ብትወጋ የሚያስገኝላትን ጥቅም እሚሙቆና አሰማምሮ በየዕለቱ የሚጽፋቸው አርቲክሎች፤ በጥቂት ቀናት ውስጥ የሕዝቡን አስተያየት ማርኮ ለጦርነቱ ተካፋይነት ደጋፊ እንዲሆን አደረገው፡፡

ሶሲያሊስቶቹ ቤኒቶን ካባረሩ በኋላ፤ ጦርነቱን ለመቃወም የጀመሩትን ትግል በአቫንቲ ጋዜጣቸው ላይ ለመቀጠል፤ ሙሶሊኒን የመሰለ የሕዝብን መንፈስ የሚቀሰቅስና የሚያሳምን ሰይጣን ጋዜጠኛ ከየት ያግኙ ? ባላሰቡትና ባልጠበቁት መንገድ ከድቷቸው፤ ከሊበራሎቹና ከናሽናሊስቶቹ ጐን ሆኖ ያደረሰባቸውን ጉዳት በምንም ዓይነት ሊቋቋሙት አልቻሉም። በመጨረሻውም የሊበራሉ መንግሥት (ዕድሜ ለሙሶሊኒ ኘሮፓጋንዳ) የሕዝቡን ድጋፍ አግኝቶ ጣልያን ከእንግሊዝና ከፈረንሣይ ጋር የጦርነቱ ተካፋይ ስትሆን፤ የሶሲያሊስቶቹን የተቃውሞ ድምፅ የሚያዳምጥና የሚከተል ሳይገኝ ቀረ። ሙሶሊኒ ራሱም ለዚሁ ጦርነት ወዶ ዘማች ሆኖ አንድ ዓመት ያህል ከተዋጋ በኋላ፤ በጦሩ ሜዳ ላይ በጽኑ ቆስሎ ለሕክምና ወደ አገሩ ተመለሰ። ቤኒቶ፤ በሚላኖ ሆስፒታል በሚታከምበትም ጊዜ፤ የኦስትሪያ-ሀንጋሪያና የጀርመን ድል መሆን፤ ከእነሱም ጋር የኦቶማን ኢምፓየር መፈራረስ፤ ለአውሮፓ አገሮችና ለሌላውም ዓለም ሕዝቦች፤ ምን ያህል ሰላም እንደሚያስገኝ በ " IL - POPOLO " ጋዜጣው ላይ ከመጻፍ አላቋረጠም ነበር።

በህዳር 1918 ዓ.ም ይህ አስቃቂ የሆነው የመጀመሪያው የዓለም ጦርነት፤ በፈረንሣይና በእንግሊዝ የጦር ኃይሎች እንዲሁም በአሜሪካ አሸናፊነት ሲፈጸም፤ ጣልያንም ከእነዚሁ ድል አድራጊዎች ጋር አባል ሆና በመሰለፏ፤ ከፍተኛ ደስታና ኩራት ተሰምቷት ነበር። ይሁን እንጂ፤ ከጦርነቱ ፍጻሜ በኋላ በቬርሣይና በሰንት ዠርመን አንላይ፤ (ST. GERMAIN-EN-LAYE) በድል አድራጊዎቹና በተሸናፊዎቹ አገሮች መካከል የሰላም ውል ሲፈረም፤ የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት ለጣልያን ገብተውላት የነበረውን ቃል ሙሉ በሙሉ ባለመፈጸማቸው፤ በጣልያን ሕዝብና መንግሥት ላይ ከፍተኛ ቅሬታ አሳደሩ። በጥንታዊው ዘመን፤ የኦስትሪያ-ሀንጋሪያ ኢምፓይሮች፤ በሰሜን በኩል ከጣልያን ላይ ነጥቀው ከወሰዱባት ግዛቶቿ ውስጥ ከሁለቱ አውራጃዎች ከትሪየስቴና ከትራንተር በስተቀር፤ ሌሎቹ እንደማይመለሱላትና፤ በአፍሪካም የነበሩትን የጀርመን የቅኝ ግዛቶች ከፈረንሣይና ከእንግሊዝ ጋር የመካፈል ዕድሉ እንደማይሰጣት ተነገራት። ፈረንሣይና እንግሊዝ የየራሳቸውን ጥቅም በማስቀደም የገቡበትን ቃል ሳያከብሩ በመቅረታቸው፤ የጣልያን ሶሲያሊስቶች ቀድሞውንም ቢሆን እነዚህን ካፒታሊስቶች አምነን የጦርነቱ ተካፋይ መሆን አልነበረብንም በማለት፤ ሕዝቡን ለማነሣሣትና የወገኖቻቸውን ቁጥር ለማበርከት የፕሮፓጋንዳ ትግላቸውን አፋፋሙ። በዚህ ጊዜ፤ ተንኮለኛው ሙሶሊኒ በዚያ ሕዝቡ በሚያደንቅበት ብዕሩ ሶሲያሊስቶቹን ተጋጠማቸው።

« ... የጣልያን ሕዝብ ስማ ! አገራችን የጦርነቱ ተካፋይ መሆኗ በዓለም የታሪክ ገጽ ላይ የሚያስከብራትና የሚያኮራት ሆኗል። እነዚህ ፈሪዎችና የጎዳ ዘበኞች የሆኑት ሶሲያሊስቶች የሚነግሯችሁን አትስሙ። ጣልያን፤ ከእንግሊዝና ከፈረንሣይ ጋር ለጦርነቱ ሳትሰለፍ ብትቀር ኖሮ፤ እነዚህ ዛሬ ድል አድራጊዎች የተባሉት አገሮች ሁሉ በሚኖራቸው ኃይል፤ አገራችንን የእነሱ ተወራጅ ያደርጓት ነበር። እንግሊዝና ፈረንሣይ ጦርነቱ ሲፈጸም ታገኛላችሁ ብለው የሰጡንን ቃል አሟልተው ባይፈጽሙልንም፤ በጀግንነት ተዋግተን ያገኘነውን የጋራ ድል አልካዱንም። ... እርግጥ አንድ ነገር ማመን አለብን። የመንግሥታችን መሪ የሆነው ጠቅላይ ሚኒስትር፤ በሰላሙ ጉባኤ ላይ እንግሊዝንና ፈረንሣይን በድፍረት ተሟግቶ ባለማሸነፉ እነሱ የሚፈልጉትን አግኝተዋል። በዚህ ተስፋ መቁረጥ የለብንም። ነገ መንግሥታችንን እና ኃይላችንን አጠናክረን ዛሬ የተፈጸመብንን በደል በእጥፍ እንደምናስከፍል ማመን አለብን ... » በሚል አቀራረብ፤ ቤኒቶ

ሙሶሊኒ በ IL - POPOLO ጋዜጣው ላይ እያሳመረና እያከታተለ የሚጽፈውን ሕዝቡ እየተሻማ በሚያነብበት ሰሞን፣ ለቤኒቶ ትግል የሚረዳ አንድ ሌላ ነገር ተፈጠረ። ጠቅላይ ሚኒስትሩ ቪቶሪዮ አርላንዶ ፓርለማ ቀርቦ፣ « ... ፈረንሣይ አገር በተከናወነው የሰላም ጉባኤ ላይ፣ ጣልያን ከድል አድራጊዎቹ ጋር የውሉ ፈራሚ መሆኗ እጅግ ቢያስደስተኝም፣ እንግሊዝና ፈረንሣይ የሰጡንን ቃል እሚልተው እንዲፈጽሙልን ተሟግቼ ለማሸነፍ ባለመቻሌ እጅግ አዝናለሁ። በዚህም ምክንያት በገዛ ፈቃዴ ሥልጣኔን እለቃለሁ ... » የሚል መግለጫ ሰጠ። ይህ የጠቅላይ ሚኒስትሩ መግለጫ፣ ጥቂት ቀደም ሲል ቤኒቶ የጻፈውን የሚያረጋግጥ በመሆኑ፣ የቀድሞዎቹ የአቫንቲ ጋዜጣ አንባቢዎች ሁሉ ወደ " IL - POPOLO " ተዛውረው የሙሶሊኒ አድናቂዎች ሆኑ።

## የቀድሞው ሶሲያሊስት ፋሽስት ሆኖ መጣ

ቤኒቶ ሙሶሊኒ፣ እ.ኤ.አ በ1915 ዓ.ም ከሶሲያሊስቶቹ ጋር ተጣልቶ ወደ ሊበራሎቹ እንደ ተለወጠው፣ አሁን ደግሞ ሊበራሎቹን አውግዞ፣ እሱ ራሱ ብቻውን የሚያዝበት " ፋሽስት " የተባለውን ልዩ የሆነ የፖለቲካ ፓርቲ መሥርቶ ብቅ አለ። በመጋቢት 1919 ዓ.ም በሚላኖ ከተማ ብዙ ሺህ ሕዝብ በተሰበሰበበት አደባባይ ላይ፣ ቤኒቶ ሙሶሊኒ ይህን አዲስ ያቋቋመውን የፋሽስት ፓርቲ ያስተዋወቀው በሚከተለው ንግግሩ ነበር።

« ... ፓርለማችን የልዩ ልዩ የፖለቲካ ፓርቲዎች መፈንጫ በመሆኑና ሥርዓት ያለው የጠነከረ የአስተዳደር መንግሥት ባለመኖሩ፣ አገራችን ጣልያን እንደ ሌሎቹ የአውሮፓ አገሮች ለመሻሻልና ለማደግ ዕድል አጥታ ትኖራለች። የሕዝብ ተወካዮች ነን ብለው በፓርለማችን የታጐሩት፣ ሶሲያሊስቶች፣ ኮሙኒስቶች፣ ሊበራሎች፣ ናሽናሊስቶች የተሰኙት ልዩ ልዩ ፓርቲዎች በሙሉ፣ በምን እንደሚረዱን ቀርበን ብናጠናቸው፣ ባጭሩ የሕዝቡን ጉዳይ ወደ ጐን ትተው የየራሳቸውን ጥቅም ከማባረር በስተቀር አንዳች ቁም ነገር ሲሠሩልን አናያቸውም። በየአምስት ዓመቱ ምርጫ በሚደረግበት ጊዜ፣ እነዚህ ሰዎች በየአደባባዩ እየዞሩ ለሕዝብ አሳቢዎች ለሕዝብ ተጨናቂዎች፣ ለሕዝብ ጥቅም መንግሥትን ተቆጣጣሪዎች በመሆን፣ የሕዝቡን የኑሮ ችግር ለማቃለል ሌት ተቀን ሠርተን እናሳያችኋለን እያሉ የሚሰጧችሁን ቃል በትክክል ታስታውሳላችሁ። ነገር ግን ምርጫውን አግኝተው በሕዝቡ ስም የፓርለማውን ወንበር ከያዙ በኋላ፣ ያ ሁሉ ያደረጉት ዲስኩር፣ ያ ሁሉ የሰጡት ተስፋ ወደ ጐን ተትቶ፣ ከአስተዳዳሪው መንግሥት ጋር እየተሻረኩ የግል ሀብታቸውን ለማዳበር የጥቅም ፕሮግራማቸውን በሰፊው ይዘረጋሉ። እስቲ ልብ ብላችሁ ተመልከቱ ! የትኛው የፓርለማ አባል ነው? ባለጸጋ ሆኖ ያልተንደላቀቀ፣ የትኛው የፓርለማ አባል ነው ? በየከተማው ፎቅ ቤትና ቪላ ያልሠራ፣ የትኛው የፓርለማ አባል ነው ? በስዊስ ባንክ ገንዘብ እያሸሸ ያላከማቸ ፣ ስለዚህ፣ ዛሬ በአለንበት ዘመን የጣልያን ሕዝብ ከመቸውም ጊዜ የበለጠ ብዙ ነገሮችን የተረዳና ያስተዋለ ስለሆነ፣ በፓርለማችን ውስጥ ታጉረው ጥቅማቸውን የሚያባርሩትን የልዩ ልዩ ፓርቲ ሰዎች የማታለያ ዲስኩር፣ ከእንግዲህ ወዲህ አይቀበላቸውም። ዛሬ የጣልያን ሕዝብ ከልቡ የሚያስብለትንና የሚሠራለትን ወኪል ለመምረጥ በቂ ችሎታ ስላለው፣ እንደ አለፉት ዘመናት አይታለልም። ስለዚህ፣ የጣልያን ሕዝብ እስከዛሬ ድረስ ፍዳ ሲቀበል ከኖረበት ከዚህ መከራ አምራች ከሆነው የሊበራል አስተዳደር ተገላግሎ፣ የሰላምና የብልጽግና

ሕይወት የሚያመጣለትን ይህንን " ፋሽስት " የተባለውን አዲስ ፓርቲ መሥርቼ ይኸው ዛሬ ለመላው የጣልያን ሕዝብ አቀርባለሁ።

.... ይህን አዲሱን ፓርቲያችንን ይዤላችሁ ስቀርብ፣ ዓላማው ምንድን ነው ? ግቡስ እስከምን ድረስ ነው ? ብላችሁ እንደምትጠይቁ አውቃለሁ። ጥያቄያችሁም ተገቢና ትክክል ስለሚሆን መልሱን ማግኘት ይገባችኋል። ከሁሉ በፊት ፓርቲያችን እስከ ዛሬ ድረስ ሶሲያሊስቶችና ሊበራሎች ሲቀልዱባችሁ እንደነበረው፣ የማይቻለውን ሁሉ እንሠራለን በማለት ብዙ ሺህ የማታለያ ተስፋ የሚያሸክማችሁ አለመሆኑን እንድትገነዘቡት እፈልጋለሁ። የፓርቲያችን ዋና ዓላማ፣ የጠነከረ የመንግሥት አስተዳደር ተቋቁሞ፣ ሕግና ሥርዓት በጥብቅ የሚከበሩበት፣ ፍርድ ሕግን ተመርኩዞ በትክክል የሚሰጥበት፣ አለቃና ጭፍራ መብትና ግዴታቸው ተለይቶ የሚታወቅበት፣ ማንኛውም የጣልያን ዜጋ የግል ነፃነቱና መብቱ የሚጠበቅበት፣ ሐቀኝነትና ታማኝነት ተገቢ ዋጋቸውን የሚያገኙበት፣ የአገር ነፃነት እንዳይደፈር፣ የአገር ክብር እንዳይዋረድ፣ መንግሥትና ሕዝብ ነቅተው ግዳጃቸውን የሚፈጽሙበት እንዲሆን የተመሠረተ ስለሆነ፣ የፋሽስት ፓርቲያችን በአጭር ጊዜ ውስጥ አገራችን ከሌሎቹ ከእነ እንግሊዝና ፈረንሣይ አገሮች ሁሉ ቀድማ የምትገኝ፣ የሕዝባችንም ኑሮ ከመታረዝና ከመጉዳት በፍጥነት ተላቅቆ ከፍተኛውን የመሻሻል ብርሃን እንደሚጐናጸፍ ላረጋግጥላችሁ እወዳለሁ .... »

እንግዲህ ከዚህ በላይ የተገለጸውን ሙሶሊኒ እጅግ በጋለ ስሜት እየተቅበጠበጠና እየጨፈረ ሲያስረዳ፣ በሚላኖ ከተማ አደባባይ የተሰገሰገው ሥፍር ቁጥር የሌለው ሕዝብ፣ በአእምሮው ሲጉላላ የቆየውንና በልቡ አከማችቶ ይዞት የነበረውን ምሬት ፈንቅሎ ስለአወጣለት፣ ምን ያህል እንደተደሰተና ምን ያህል እንደተማረከ፣ የሚያሰማው ጩኸትና ጭብጨባ መጠን አልነበረውም። በሙሶሊኒ የተፈጠረው ይህ የፋሽስት ፓርቲ፣ በዚህ ዓለም ከዚህ ቀደም ተሰምቶ የማይታወቅ አዲስ ታሪክ መስሎ ስለተገመተ፣ ሕዝቡ አባል ሆኖ ለመመዝገብና መዋጮውን ለመክፈል የሚያደርገውን እሽቅድድም፣ የፓርቲው ጸሐፊዎች እየተቀበሉ ለማስተናገድ አቅቷቸው ነበር። ወዲያው ብዙ ቀን ሳይቆይ የአዲሱ የፋሽስት ፓርቲ ጽሕፈት ቤት በሚላኖ ከተማ በአንድ ትልቅ ሕንፃ ውስጥ ተደራጅቶ ከተቋቋመ በኋላ፣ በየዕለቱ የአባሎቹ ቁጥር እየጨመረ፣ ለፓርቲው የሚሰጠውም የመዋጮ ገንዘብ እጅግ እያደገ ሲሄድ፣ ቀደም ሲል ሙሶሊኒ ያቋቋመውም " IL - POPOLO " የተባለው ጋዜጣ፣ የፋሽስት ፓርቲ አፈጉባዔ ሆኖ ከሌሎቹ ጋዜጦች ሁሉ የበለጠ ተነባቢ ሆነ። የሕዝብን መንፈስ በመቀስቀስና በማሳመን የታወቀው ዲስኩረኛ ቤኒቶ ሙሶሊኒ፣ አዲሱ የፋሽስት ፓርቲ ለጣልያን ሕዝብ የሚያስገኝለትን የሰላምና የብልጽግና ሕይወት በየአደባባዩ እየዞረ ተንትኖ ሲያስረዳ፣ አብሮት የሚጮኸውና የሚጨፍረው ሕዝብ ብዛት ከዚህ ቀደም የታየ አልነበረም።

ሙሶሊኒ ይህን ሁሉ የሕዝብ ቅስቀሳ በሚያደርግበት ጊዜ፣ የነ ጂዮሊቲ መንግሥት ደጋፊዎች፣ ሊበራሎቹም ሆኑ ናሽናሊስቶቹ " ሙሶሊኒ ዕብድ ነው " እያሉ ችላ ከማለት በስተቀር፣ አንድ ቀን ባልጠበቁት መንገድ አናታቸው ላይ ወጥቶ ሥልጣናቸውን ቀምቶ እንደሚያባርራቸው ጨርሶ አልታያቸውም ነበር። የሙሶሊኒን አደገኛነት ደህና አድርገው የተረዱትና ምናልባትም አገሩን በጥብጠ ሊያጠፋን ይችል ይሆናል፣ የሚል ሥጋት ያደረባቸው ሶሲያሊስቶቹ ብቻ ነበሩ። በ1915 ዓ.ም፣ ሙሶሊኒ በዓለም ጦርነት ውስጥ የጣልያንን ተካፋይነት



የኢትዮጵያ ጠላት፤ ቤኒቶ አምሊካር አንድሬአ ሙሶሊኒ

ከሊበራሎቹ ጋር ደግፎ የሶሲያሊስቶቹን ዓላማ በመካዱ፤ በንዴት ተገፋፍተው የወሰዱበት እርምጃ ብዙ ቂም ስላስከተለ፤ ከአራት ዓመት በኋላ ነገሩን ሲያዩት የማይቋቋሙት ኃይለኛ ጠላት ሆኖ ቀረበባቸው። በመሠረቱ፤ ቤኒቶ ሙሶሊኒ የፋሽስትን ፓርቲ አቋቁሞ የትግሉን ዘመቻ የከፈተው፤ ጠላቶቹን ሶሲያሊስቶቹንና የኮሙኒስት ዝንባሌ ያላቸውን ብቻ ሳይሆን፤ ከጦርነቱ ጊዜ ጀምሮ የተባበራቸውን ሊበራሎቹንና ናሽናሊስቶቹንም አጥፍቶ ብቻውን ሥልጣን ለመያዝ ስለሆነ፤ ከማንም ወገን ጋር ምንም ዓይነት የመግባቢያ ድርድር ላለማድረግ የቆረጠ ነበር።

## ከመንደር ወሮበላነት ወደ አገር መሪነት

ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፤ ቤኒቶ ሙሶሊኒ በተወለደ በአሥራ ሦስት ዓመቱ በሮማኛ አውራጃ የሚገኘው የሳሌዚያኖ የቄሶች ኮሌጅ የነፃ ትምህርት ዕድል በነፈገው ጊዜ፤ « **እነዚህ ቄሶች አንድ ቀን እኔን የሚፈሩበት ጊዜ ይመጣል** » ሲል የተበሳጨ ስሜቱን ለእናቱ ገልጾላት ነበር ይባላል። እንደዚሁም አባቱ አሌሣንድሮ « ... **ልጄ አንድ ቀን የጣልያን መሪ ሆኖ ታዩታላችሁ** ... » እያለ፤ የሚታየውን ምኞት በየቦታው እየደጋገመ ይናገር እንደነበረ ተጠቅሷል። ይሁን እንጂ፤ ቤኒቶ በወጣትነቱ ዘመን ከፍተኛ የአካዳሚ ትምህርት ያላገኘ፤ ወይም ደግሞ በማንበብና በመመራመር አእምሮውን ያላነፀ ከመሆኑም በላይ፤ እጅግ አስቸጋሪ ከሆነው ጠባዩ ጋር በአናርኪስትነትና በወሮበላነት ተግባር የታወቀ ስለነበረ፤ እንኳንስ ለአገር መሪነት፤ ለተወለደበትም ቀበሌ እንኳ ተጠሪነት ይመረጣል ተብሎ የሚታሰብ ሰው አልነበረም።

እ.ኤ.አ በመጋቢት 1919 ዓ.ም፤ በሚላኖ ከተማ የመሠረተውን ይህን የፋሽስት ፓርቲ፤ ከሐያ ወራቶች በኋላ፤ በህዳር 21 ቀን 1921 ዓ.ም መንግሥትን አስጨንቆ ሕጋዊ ዕውቅና ለማግኘት ቻለ። ከዚህም አያይዞ ከፓርቲው ጋር የተጣመረ የሠርቶ አደሩን ሕዝብ መብት የሚጠብቅ የጣልያን የሠራተኞች አንድነት ማህበር ማቋቋሙን አስታወቀ። የሙሶሊኒን የፋሽስት ፓርቲ፤ የሊበራሉ መንግሥት ሕጋዊነቱን ካረጋገጠለት ከስድስት ወራት በኋላ፤ የአባላቱ ቁጥር ሲመሠረት ከነበረው ከሠላሳ ሺህ (30.000) ወደ ሰባት መቶ ሺህ (700.000) መድረሱ ተነገረ። ከእነዚህም አባሎች መካከል ዋና ዋና የመንግሥት ሹማምንቶችና የጦር አለቆች፤ ኢንዱስትሪያሊስቶችና ከበርቴዎች የተመዘገቡ መሆናቸው በይፋ ተገለጸ። የፓርቲው ዋና አዛዥ የተከበሩ ሲኞር ቤኒቶ ሙሶሊኒም፤ ለታጋይነታቸውና ለመሪነታቸው አንድ ልዩ የመጠሪያ ስም ተፈልጐ እንዲሰጣቸው ጥናት ከተደረገ በኋላ፤ " ዱቼ " እንዲባሉ ተወሰነ። " ዱቼ " የተባለው ቃል ትርጉሙ መሪያችን ወይም ጌታችን ማለት ነው።

በዚህ አኳኋን አለመጠን እየገሠገሠ የመጣው የፋሽስት ፓርቲ፤ ሦስት ዓመት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ ወደ አንድ ሚሊዮን የሚቆጠሩ አባላትን ስለአቀፈና በሕዝቡም ዘንድ ተደናቂነቱ እየገነነ ስለሄደ፤ የሚቀጥለው እርምጃ በሊበራሎች የሚመራውን የነ ጂዮሊቲን መንግሥት አባርሮ፤ ሥልጣኑን " ዱቼ " እንዲረከብ ማድረግ ብቻ ነው ተብሎ ተወሰነ። ለዚህም ግብ በቅድሚያ የሚያስፈልገው ዝግጅት፤ ቁጥራቸው እስከ ሦስት መቶ ሺህ የሚጠጉ (300.000) ጥቁር ሸሚዝ ለባሾች የሆኑትን ወጣት ፋሽስቶችን በውትድርና ማሠልጠንና ማስታጠቅ ነበር። የሠራዊቱም ሥልጠና ከተጠናቀቀ በኋላ፤ የ1922 ዓ.ም ከማለቁ በፊት ሙሶሊኒ

በተዋጊዎቹ ታጅቦ ወደ ሮማ በመጓዝ፣ አዲሱን የፋሽስት መንግሥት የሚያቋቁምበትን ፕሮግራም ማዘጋጀት ጀመረ።

በሚላኖ ከተማ የዱቼ ዝግጅት በሚጧጧፍበት ሰዓት፣ በሮማ ንጉሥ ቪክቶሪዮ አማኑኤል ዣልሳዊና የመንግሥቱ መሪዎች እነ ጂዮቫኒ ጂዮሊቲ፣ አንቶኒዮ ሳላንድራ፣ ሉዊጂ ፋክታ፣ በየዕለቱ እየተሰበሰቡ፣ ከዚህ ከሚዘጋጅባቸው የፋሽስት አደጋ ለመዳን፣ ሙሶሊኒ ተጠርቶ አንድ የካቢኔ ሚኒስትርነት ቢሰጠው ይሻላል በሚል ሐሳብ ከስምምነት ላይ ደረሱ። እነዚህ ጊዜው የከዳቸው የፖለቲካ መሪዎች፣ በጣልያን የክረምት መግቢያ ፀሐይ ላይ እያንገዋበበ የመንግሥቱን ሥልጣን አስገድዶ ለመንጠቅ የሚመጣው ዱቼ ሙሶሊኒ፣ ከጠቅላይ ሚኒስትርነት በስተቀር በምንም ዓይነት የካቢኔ ሚኒስትርነትን እንደማይቀበል አልተረዱትም። ባጭር ጊዜ ውስጥ የፋሽስት እርምጃ እዚህ ደረጃ ላይ የደረሰው፣ ሙሶሊኒን ዕብድ አድርጉ በመገመትና ዞሮ ዞሮ የት ሊደርስ ይችላል ? እያሉ ችላ በማለታቸው መሆኑ አልገባቸውም። በተጨማሪም የመንግሥቱ ዋና ዋና ሹማምንቶች፣ የጦር አዛገኖችና መኮንኖች፣ የፖሊስና የፀጥታ ኃላፊዎች ሁሉ፣ የሙሶሊኒ ደጋፊዎች መሆናቸውን አልሰሙም። ዘወትር በኩሪናሌ ቤተመንግሥት በንጉሡ ቢሮ እየተሰበሰቡ፣ ትክክለኛ ባልሆኑ መረጃዎች ላይ እየተመሠረቱ የፋሽስቶቹ መሪ ሥልጣን ካልወሰድኩ ብሎ እስከዚህ ሊደፍረን አይሞክርም እያሉ ሲራቀቁ፣ ጥቅምት 24 ቀን 1922 ዓ.ም ሙሶሊኒ የመንግሥቱን ሥልጣን ለመረከብ፣ ከሚላኖ እስከ ሮም በሚጓዝበት ጊዜ የሚከተሉት ዝግጅቶች በፕሮግራም ተዘርዝረው ተገለጡ።

1. ከመላው ጣልያን ተመልምለው፣ በጥሩ ሁኔታ የሠለጠኑት እስከ ሦስት መቶ ሺህ የሚደርሱት ባለ ጥቁር ሸሚዝ የፋሽስት መለዮ ለባሾች ከሚላኖ ወደ ሮም ጉዞ እንዲጀምሩ ተደረገ።

2. እነዚህ በቅድሚያ ጉዞ የጀመሩት የፋሽስት ሠራዊቶች፣ ሙሶሊኒ ከሚላኖ ከመነሣቱ በፊት፣ በሮም አካባቢ የሚገኙትን ከተሞች፣ እንደ እነ ቼቪታቬኪያ፣ ሳንታ ማሪኔላ፣ ቲቮሊ የመሳሰሉትን ሁሉ በራሳቸው ሥልጣን ይዘው እንዲጠብቁ ታዘዙ።

3. የሮማ መንግሥት የጦር ሹማምንቶች ሁሉ ምንም እንኳ ለፋሽስት ፓርቲና ለዱቼ ድጋፋቸውን በቅድሚያ የሰጡ ቢሆንም፣ ሬቮሉሽኑ የሕዝብ ነው እንዲባል፣ ሙሶሊኒ ወደ ሮም በሚያደርገው የጉዞ ፕሮግራም ላይ፣ ተካፋይ ሳይሆኑ በገለልተኝነት እንዲመለከቱ ተነገራቸው።

4. ጥቅምት 28 ቀን 1922 ዓ.ም ክቡር ዱቼ ከሚላኖ በሰጠው መግለጫ፣ « .... እኛ ፋሽስቶች ሕዝቡ ስለጠየቀን የመንግሥቱን ሥልጣን ለመረከብና መላ ጣልያንን ለማስተዳደር ዝግጁ ነን። ሥልጣኑንም የምንቀበለው ፊት ለፊት በሮማ አደባባይ ገብተን ነው እንጂ፣ በጓዳ በር አይደለም። ይህም በመልካም እንዲፈጸም፣ አሁን ያለው መንግሥት ሥልጣኑን በሰላምና በወግ ሊያስረክበን ይገባል። አለበለዚያ እኛው ራሳችን በሰልፍ ሮማ ሄደን ሥልጣኑን እንወስደዋለን .... » ሲል የመጨረሻ ማስጠንቀቂያውን ሰጠ።

5. ይህ ማስጠንቀቂያ በሮም ከተማ ላይ ሳይታሰብ ከሰማይ እንደወረደ በንብ ሲፈነዳ፤ ጠቅላይ ሚኒስትሩና ዋና ዋናዎቹ የፓርላማ መሪዎች በንጉሡ ዙሪያ ተሰብስበው ምን ማድረግ ይሻላል ? እያሉ በሚወያዩበት ሰዓት፤ ከካቢኔው ሚኒስትሮች አብዛኛዎቹ፤ የፋሽስቱ የዱቼ ደጋፊዎች ሆነናል በማለት የሥራ መልቀቂያቸውን አቀረቡ። እንግዲህ! የመንግሥቱ ጠቅላይ ሚኒስትር ብቻውን ያለ ሚኒስትሮች ባዶ በሆነ ካቢኔ የሚሠራው ነገር ስለሌለ፤ ንጉሥ አማኑኤል ሳልሣዊ ሲኞር ዱቼ ሙሶሊኒን በወግ ጠርተው፤ የጠቅላይ ሚኒስትርነቱን ሹመት እንዲሰጡ አስፈላጊ መሆኑን ሁሉም ተስማሙ። ወዲያውም ግርማዊ የጣልያን ንጉሥ፤ ሲኞር ሙሶሊኒ ወደ ሮም መጥተው ሥልጣኑን እንዲቀበሉ ትሕትና በተመላበት ቋንቋ በቴሌግራም ጥሪያቸውን አስተላለፉ።

6. ዱቼ ለሰላሙም ሆነ ለጠቡ አስቀድሞ በሚገባ የተዘጋጀበት ስለሆነ፤ በብዙ ሺህ የሚቆጠሩ ጥቁር ሸሚዝ ለባሾቹን አስከትሎ፤ ጥቅምት 30 ቀን 1922 ዓ.ም በባቡር ተጉዞ ከጠዋቱ በአራት ሰዓት ተኩል ሮም ደረሰ። ከዚያም በከፍተኛ አጀብ ወደ ኩሪናሌ ቤተመንግሥት አምርቶ፤ ከንጉሡ ጋር ለአምሳ ስምንት ደቂቃዎች ፕሮቶኮላዊ የሆነ የሐሳብ ልውውጥ ካደረገ በኋላ፤ የጠቅላይ ሚኒስትርነቱን ሥልጣን ተቀብሎ ለማረፊያ ወደተዘጋጀለት ወደ ሳቮያ ሆቴል ሄደ።

በዚህ በጣልያን ታሪክ ውስጥ አዲስ ምዕራፍ በተከፈተበት በጥቅምት 30 ቀን 1922 ዓ.ም፤ ሕዝቡ የፋሽስትን መዝሙር እየዘመረ በየአደባባዩ ድምፁን ሲያሰማና ሲጨፍር፤ ዱቼ ሙሶሊኒ ምን ዓይነት ዳቦ ይዞለት እንደመጣና ወደፊትም ምን ዓይነት ሕይወት እንደሚገነባለት በትክክል የሚያውቀው ነገር አልነበረውም። በየትኛውም ዓለም የሚኖር ሕዝብ፤ ትክክለኛ ፍርድና የተሟላ ሕይወት እሰጥሃለሁ ብሎ ለሚቀርብለት መሪ፤ ያለ እንዳች ገደብ አጨብጭቦ መቀበሉ የተለመደ ቢሆንም፤ የጣልያን ሕዝብ ለፋሽስቱ ዲክታተር መሪ የገለጸው ደስታ፤ ከስልሳ ዓመታት በፊት እነ ካቩርና እነ ጋሪባልዲ፤ (CAVOUR-GARIBALDI) የአገሪቱን አንድነት በመመሥረት ከፍተኛ ድል ባስገኙ ጊዜ፤ ከተደረገው በዓል የበለጠ ሆኖ መታየቱ፤ የዓለምን ሕዝብ እጅግ አስደንቋል።

በዚህ በሙሶሊኒ ሥልጣን መያዝ ጉዳይ ሌላው እጅግ አስገራሚና በጣልያን የፖለቲካ ታሪክ ላይ ትልቅ ትዝብት ሆኖ የተመዘገበው፤ ለብዙ ዓመታት አገሪቱን ይመሩ የነበሩት እነ ጂዮሊቲ፤ በጉልበቱ ወንበራቸውን አስለቅቆ ለወሰደባቸው ዲክታተር፤ በፓርለማው አዳራሽ የሞቀ ድጋፋቸውን ሲያበረክቱ መታየታቸው ነው። « ... በጣልያንነቱ የሚኮራ፣ የአገራችንን ታሪክ የሚያከበር፣ ሕዝባችንን ወደተሻለ ሕይወት ለመምራት ቆርጦ የተነሣ መልካም መሪ አገኘን ... » በሚል ቃል በጋለ ዲስኩር የተቀበሉት በምን ምክንያት ነው ? ተብሎ ቢጠየቅ፤ መልሱ በማይጠረጠር ከፍርሃትና ራስን ለማዳን ከመጨነቅ የተነሣ መሆኑን ማመን ይቻላል። እነሱ ግን እንደዚህ ነው ብለው አያምኑም። አንድ የፖለቲካ ሰው ለአገር ዕድገትና ለተሻለ አስተዳደር መልካም ሐሳብ ይዞ ሲቀርብ፤ በተስፋ መቀበልና መደገፍ የዴሞክራሲ ትክክለኛው ትርጉሙ ነው ብለው ደካማነታቸውን ለመሸፈን ጥረዋል። ይህ ሁሉ ውሸት ነው። በዚያ በጥቅምት 30 ቀን 1922 ዓ.ም ጣልያንን

አስጨንቆ በዲክታተር አመራር ለመግዛት ከሊበራሎቹ ላይ ሥልጣን ቀምቶ የያዘው ሰው ማን ነበር ? ቢባል፤

- ያ – ወደዚህ ዓለም ከመጣበት ዕለት ጀምሮ እልኸኛና ቀጭባራ በሆነው ጠባዩ፤ እናቱን እያሰቃየ ያደገው ልጅ፣
- ያ – የትምህርት ቤቶቹ ተደባዳቢና በጥባጭ በመሆን መምህራኖቹንና ጓደኞቹን እጅግ ሲያስቸግር የነበረው ተማሪ፣
- ያ – በሮማኛ አውራጃ የሰፈር ወርበላ ሆኖ ከሽማግሌዎችና ከአሮጊቶች ላይ ገንዘብ እየቀማ፤ ሰላም ሲነሣ የነበረው ሥራ ፈት፣
- ያ – አናርኪስት በሆነው ምግባሩ በየከተማው የሚኖረውን ሕዝብ ፤ ሲያፋጅና ሲያማታ በፖሊስ እየተያዘ በየጊዜው ይታሰር የነበረው በጥባጭ፣
- ያ – በየተሰደደባቸው አገሮች ዓድማ አዘጋጅና ተንኮል አርቃቂነቱ እየተደረሰበት፤ በፖሊስ ተይዞ ይባረር የነበረው አናርኪስት፣
- ያ – በፖለቲካ ጉዳይ ዛሬ የደገፈውን ነገ የሚቃወም፤ ዛሬ የተቃወመውን ነገ የሚደግፍ፤ በዕምነቱ የማይፀና ከዳተኛና ቀጣፊ እየተባለ በየፓርቲዎቹ በመወገዝ የታወቀው ሰው፣

## ቤኒቶ - አምሊካር - አንድሬአ - ሙሶሊኒ

ነው እንጂ፤ ሌላ ሙሶሊኒ ተብሎ የሚጠራ አዲስ ፍጡር አልነበረም።

**መረጃ፤** ከዚህ በላይ የቀረበውን የሙሶሊኒን ታሪክ ደራሲው በሰፊው ጥናቱን ያካሄደው፤ በጣልያን አገር እ.ኤ.አ ከ1972 ዓ.ም እስከ 2004 ዓ.ም ድረስ ለሠላሣ ሁለት ዓመታት በኖረበት ዘመን ውስጥ መሆኑን ለአንባቢዎቹ ይገልጻል።

# ምዕራፍ ፭

## ቤኒቶ ሙሶሊኒ ከፈረንሣይና ከእንግሊዝ ጋር

ጥቅምት 30 ቀን 1922 ዓ.ም የፋሽስቱ መሪ ሥልጣን ይዞ መንግሥት ባቋቋመ ጊዜ፤ የፈረንሣይ ሬፑብሊክ መሪዎች የጣልያን ሕዝብ የደስታ ተካፋዮች አልነበሩም። እንዴት በአውሮፓ ዴሞክራሲ በሰፈነበት ምድር ላይ፤ ፋሽስት የተባለ የዲክታተር አስተዳደር ሊቋቋም ይችላል? በሚል ተቃውሞ፤ የፈረንሣይ መንግሥት በቤኒቶ ሙሶሊኒ ላይ የሚያሳየው ንቀትና ቸልታ ለብዙ ዓመታት የቀጠለ ሆነ። ሙሶሊኒ ግን፤ ምንም ዓይነት ቅሬታ ያላደረበት መሆኑን እያሳየ ከፈረንሣይ ጋር ሊኖረው የሚገባውን ግንኙነት በወዳጅነት ለመገንባት ብዙ ጥረት እያደረገ ለአሥራ አንድ ዓመታት ታግሶ ቆይቷል።

የእንግሊዝ መንግሥት ደግሞ፤ የሙሶሊኒ ሥልጣን መያዝ የወታደር ኩዴታ ሳይሆን የሕዝብም ድጋፍ የታየበት ስለሆነ፤ አዲስ ከተቋቋመው ከፋሽስት መንግሥት ጋር ቀድሞ የነበረንን መልካም ግንኙነት ከመቀጠል መለወጥ የለብንም ብሎ ስለወሰነ፤ የደረሰ ችግር አልነበረም። ይልቁንም የፋሽስት መንግሥት ከተቋቋመ ከስድስት ወራት በኋላ፤ ግርማዊ የታላቋ ብሪታንያ ንጉሥ ጆርጅ አምስተኛ፤ ጣልያንን በኦፊሲየል ለመጎብኘት በመጡ ጊዜ፤ የሙሶሊኒ አቀባበልና አክብሮት የሞቀ በመሆኑ እንግሊዞች ሳይደሰቱ አልቀሩም። እንዲሁም የፋሽስት መንግሥት ጣልያንን በመምራት የአምስት ዓመት ዕድሜ እንዳሳለፈ፤ በ1927 ዓ.ም በዚያን ጊዜ የእንግሊዝ መንግሥት ካቢኔ የገንዘብ ሚኒስትር የነበረው ዊንስቶን ቸርችል፤ ሮም ሄዶ የሰጠው አስተየየት በታሪክ ሲጠቀስ የቆየ ሆኗል። የእንግሊዝ የገንዘብ ሚኒስትር ከፋሽስቱ መሪ ጋር በፓላሶ ቬኔስያ (Palazzo-Venezia) በሰፊው ከተነጋገረ በኋላ በሰጠው መግለጫ፤ « ... እኔ ጣልያን ብሆን፤ ከዱቼ ጋር ያለ አንዳች ማመንታት እሰለፍ ነበር። ታላቁ መሪያችሁ ሙሶሊኒ፤ አንድ ሕዝብ በተፋጠነ መንገድ እንዴት ሊራመድና ራሱን ለከፍተኛ ደረጃ ለማብቃት እንደሚችል፤ ያሳየው የአሠራር ዘዴ፤ እነዚያን ከይሲዎች የሆኑትን የራሽያን ኮሚኒስቶች የሚያሳፍር ነው .... » ብሏል።

ሲኞር ሙሶሊኒ፤ ከታላቋ ብሪታንያ ጋር ወዳጅነቱን በመልካም ግንኙነት ካስፋፋ በኋላ፤ ከፈረንሣይ መንግሥት በኩል የሚደረግበትን ጥላቻና ንቀት ከቁም ነገር አልቆጠረውም። የፈረንሣይ ጋዜጦችም በየጊዜው የሚያወርዱበት ዘለፋና ስድብ አላሠጋውም። ይልቁንም የፈረንሣይ ከአውሮፓ ጉዳይ መራቅ ባዶ ቦታ ስለሰጠው፤ ከእንግሊዞች ጋር እየተቀራረበ ለወደፊቷ አውሮፓ ዕድል ተጨናቂና የሰላም ፕላን አውጭ ሆነ።

እ.ኤ.አ ጥቅምት 17 ቀን 1932 ዓ.ም ስለ አውሮፓ የወደፊት የፖለቲካ አቋም ሙሶሊኒ በፀነሰው አዲስ ፕላን፤ በገኔቭ የመንግሥታት ማህበር አራቱ የአውሮፓ ታላላቅ አገሮች፤ እንግሊዝና ፈረንሣይ፤ ጣልያንና ጀርመን፤ አንድ ክበብ

አቋቁመው ስለ ዓለም ሰላምና ደህንነት እየተወያዩ አብረው ቢሠሩ ከፍተኛ ጥቅም የሚገኝበት መሆኑን አስረዳ። እንደሚታየው ይህ የሙሶሊኒ ፕላን በማናቸውም የዓለም ጉዳይ ላይ ጣልያን፣ ከእንግሊዝና ከፈረንሣይ መንግሥታት ጋር እኩል ተቆጥራ ከፍተኛ ሚና ለመጫወት የሚያስችላትን መንገድ ለማግኘት መሆኑ ግልጽ ነበር። እንግሊዞች ገና ከጠዋቱ በጣልያን አገር ለተመሠረተው የፋሽስት መንግሥት መልካም አስተያየታቸውን ያላሳደሉ በመሆናቸው፣ ዱቼ ያቀረበውን ፕላን በክፉ ዓይን አልተመለከቱትም። ፈረንሣይም ምንም እንኳ ካለፉት አሥር ዓመታት ጀምሮ የጣልያን ዋና ከተማ ሮም፣ ከፓሪስና ከሎንዶን እኩል የአውሮፓ የፖለቲካ እንቅስቃሴ የሚካሄድባት ከተማ እንድትሆን የፋሽስቱ መንግሥት የሚያደርገውን ጥረት ሳትቀበል የኖረች ብትሆንም፣ ከ1933 ዓ.ም ጀምሮ የሙሶሊኒ ዕድገት እየጨመረ መሄዱ ስለአሠጋት፣ ሐሳቧን ማሻሻል ወይም መለወጥ ግዴታ ሆነባት። የፈረንሣይ ልዩ ልዩ የፖለቲካ መሪዎችም፣ በሙሶሊኒ እና በፋሽስት ፓርቲ ላይ ይነዙት የነበረውን የአጥቂ ፕሮፓጋንዳ ለውጠው፣ ከጣልያን ጋር ተራርቀን መኖር ጉዳቱ የጋራችን ስለሆነ፣ ተቀራርበን መሥራት አለብን የሚል አቋም ያዙ። በተለይም በጥር 1933 ዓ.ም (እ.ኤ.አ) አዶልፍ ሂትለር በጀርመን ምርጫውን አሸንፎ የናዚን መንግሥት ሲያቋቁም፣ ፈረንሣዮች ከሙሶሊኒ ጋር በወዳጅነት መቀራረብ እጅግ አስፈላጊ መሆኑ ታያቸው።

ናዚዎች የጀርመንን አስተዳደር በእጃቸው ከማድረጋቸው በፊት፣ ሥልጣን ለመያዝ በሚጥሩበት ጊዜ፣ ሮም እየተመላለሱ ከዱቼ ትምህርት ሲወስዱና ከፋሽስቶች ጋር በወዳጅነት ተቀራርበው ሲተጋገዙ የቆዩ በመሆናቸው፣ ሙሶሊኒ በሂትለርና በዴሞክራቶቹ አገሮች (በፈረንሣይና በእንግሊዝ) መካከል ከፍተኛ ሚና እየተጫወተ የራሱን ጥቅም ለማዳበር ትልቅ ዕድል የሰጠው መሆኑን በይበልጥ ተገነዘበ። እንዲሁም ዲክታተሩ ፋሽስት፣ በዚህ ዓይነት በጀመረው ጉዞ፣ ወደፊት የሚፈልገውን ሁሉ ለማድረግ የእንግሊዝና የፈረንሣይ ተቃውሞ እንደማይገጥመው ሙሉ ተስፋ አደረገ።

ፈረንሣዮቹም በበኩላቸው፣ ከእንግዲህ ወዲህ ከሙሶሊኒ ጋር በወዳጅነት መቀራረብ እጅግ አስፈላጊያቸው መሆኑን ስለተረዱት፣ እንኳንስ የቀኞቹ የፖለቲካ ፓርቲዎች ይቅሩና፣ ከግራ ክንፎቹም የታወቁት ራዲካሎች እነ ኤድዋርድ ሔሪዮ ጭምር፣ ለፋሽስቱ መንግሥት በር መክፈት ይገባናል የሚል አስተያየት ሰጡ። የፈረንሣይ ጋዜጦችም የፖለቲካ ፓርቲዎቹን አቋም በመከተል፣ በየቀኑ ሲያዘንቡት የነበረውን የስድብ ውርጅብኝ በአንድ ጊዜ አቁመው፣ ጣልያን ከጥንታዊው ዘመን ጀምሮ ከፈረንሣይ ጋር ያላትን የታሪክ፣ የባህልና የሥልጣኔ ግንኙነት እያራገቡ መጻፍ ጀመሩ።

እንግሊዞች ግን፣ በፋሽስት መቋቋም ጉዳይ በፈረንሣዮች ዘንድ የታየው፣ የልዩ ልዩ የተቃውሞ ሐሳብ መገለባበጥና መተረማመስ አልደረሰባቸውም። ገና ከጠዋቱ ሙሶሊኒ ሥልጣን በወሰደ ጊዜ፣ እንደ ፈረንሣዮች ችክ ብለው ዲክታተሩን ለማውገዝና ከጣልያን ጋር የነበራቸውን ግንኙነት ለማዳከም አልፈለጉም። የፋሽስቱ መንግሥት በየዕለቱ ሥልጣኑን እያጠነከረ በሚጓዝበት ጊዜ፣ አንዳንዶቹ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ሚኒስትሮችና ጓላም ጠቅላይ ሚኒስትሩ ጭምር፣ ሮም ድረስ እየተጓዙ ስለ አውሮፓና በተለይም ስለ ጀርመን ጉዳይ ከዱቼ ሙሶሊኒ ጋር መወያየታቸውን አላቋረጡም ነበር። ስለዚህም፣ አደገኛው ሂትለር በጀርመን ላይ ሲነግሥ፣ የጣልያን ፋሽስቶች ከጀርመን ናዚስቶች ጋር እንዳይሰለፉ ለማድረግ

እንግሊዞች ሙሶሊኒን በሚያነጋግሩብት ጊዜ፣ እንደ ፈረንሣዮች ትሕትና ማብዛትና መቅለስለስ አላስፈለጋቸውም ነበር። ፈረንሣዮች፣ ለአሥር ዓመታት ያህል ሲንቁትና ሲነቅፉት የኖሩ በመሆናቸው፣ ዛሬ ወዳጅነቱ ባስፈለጋቸው ጊዜ ከሙሶሊኒ መንግሥት ጋር ሲደራደሩ እንደ እንግሊዞቹ ልበ ሙሉ ሆነው ሐሳባቸውን ለማሳመን አላስቻላቸውም። ብልሁም ዲክታተር፣ የአሁኑን የፈረንሣይ ልብ ደህና አድርጐ ስለገመተውና ያለፈውንም ቂም ሊረሣው ስላልፈለገ፣ ለሉንዶኑ መንግሥት የጋለ አክብሮቱን በሞቀ መንፈስ ሲገልጽ፣ ለፓሪሱ መንግሥት የኩራት ስሜቱን ከማሳየት አልተቆጠበም። በፖለቲካ ዓለም፣ የተከበረ መቼ እንደሚወድቅ፣ የተናቀ መቼ እንደሚያድግ፣ መተንበይ አስቸጋሪ ስለሆነ፣ ፈረንሣዮች ሙሶሊኒን ጓደኛችን ሆኖ መቆም አይችልም ብለው እንደዚያ ሲያጥላሉት፣ ከአሥር ዓመታት በኋላ ኃይሉንና አደገኛነቱን አስገንዝቦ እንዲያከብሩት አስደረጋቸው።

እ.ኤ.አ በጥር ወር 1933 ዓ.ም ጀርመን በሂትለር እጅ ስትወድቅ፣ ጣልያን በሙሶሊኒ ከተያዘች ከአሥር ዓመት በላይ ሆኗት ነበር። በእነዚህ በሁለቱ ዲክታተሮች መካከል የአሥር ዓመታት የኤክስፔሪያንስ ልዩነት ስላለ፣ ሙሶሊኒ ሂትለርን በበታችነት በመቁጠር፣ ሂትለርም ሙሶሊኒን በበላይነት በማየት ስለሚተሳሰቡ፣ ሊበራሎቹ እንግሊዝና ፈረንሣይ የፋሽስቱ መሪ ናዚስቱን ይቆጣጠርልናል የሚል ተስፋ አደረባቸው። ሙሶሊኒም በዚህ ማህል ያለው ጨዋታ ምን ያህል እንደሚጠቅመው ስለገባው፣ ሂትለርን ወንድሜ ! ወገኔ ! እያለ በማስጠጋት፣ እንግሊዝና ፈረንሣይን በአንድ በኩል እያስፈራራ፣ በሌላ በኩል አይዟችሁ ወገናችሁ ነኝ በማለት እያታለለ፣ ብዙ ጊዜ የፖለቲካ ካርታውን ሲያማታ ቆየ። ውጤቱ ወደፊት ይታያል።

# ምዕራፍ ፲

## ሙሶሊኒ ከኢትዮጵያ ጋር

ቤኒቶ ሙሶሊኒ በዚህ ዓለም ኢትዮጵያ የምትባል ነፃ መንግሥት መኖርዋን ለመጀመሪያ ጊዜ የሰማው፤ እ.ኤ.አ መጋቢት 2 ቀን 1896 ዓ.ም ኮሎኒያሊስት ጣልያን ከአፄ ምኒልክ ጋር አድዋ ላይ በገጠመው ጦርነት፤ ድል ሆኖ ከፍተኛ ውርደት መቀበሉን የዓለም የዜና ማሠራጫ ድርጅቶች ሲያስተጋቡ ነው።

በዚያን ዘመን ቤኒቶ የአሥራ ሦስት ዓመት ልጅ ነበር። የቤኒቶ አባት አሌሣንድሮ ሙሶሊኒ፤ የጣልያንን መንግሥት በጠቅላይ ሚኒስትርነት የሚመራውን ሊበራሉን ፍራንቼስኮ ክሪስፒን በመቃወም ከሶሲያሊስቶቹ ጋር ሆኖ፤ የሚያደርገው ትግል ወሰን አልነበረውም። በ1896 ዓ.ም የክሪስፒ መንግሥት ኢትዮጵያን ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ ጦር አዘጋጅቶ ሲልክ፤ አሌሣንድሮ ሙሶሊኒ፤ ከተቃዋሚዎቹ ወገኖች ጋር ሆኖ የሠራተኛውን ክፍል በማሳደም፤ ወታደሮቹን ወደ ናፖሊ የመርከብ ወደብ የሚያጓጉዙትን ባቡሮች ሐዲዱን ሰብሮ ለማገድ ብዙ ሙከራ አድርጐ እንደነበረ ተነግሮለታል። በመጨረሻም ያንን ሁሉ የጣልያን ጦርና ወታደር አፄ ምኒልክና ጀግኖቻቸው አድዋ ላይ ድል አድርገው እንዳዋረዱት፤ በመላው የአውሮፓ አገሮች ጉድ እየተባለ ሲነገር፤ የክሪስፒ መንግሥት ተቃዋሚዎች የሆኑት አሌሣንድሮ ሙሶሊኒና ጓደኞቹ በየመንገዱ እየዞሩ ድል አድራጊው ምኒልክ ለዘለዓለም ይኑር (Viva-Menelik) የሚል ጩኸት ያሰሙ እንደነበረ፤ እንደ እነ ማክስ ጋሎ (Max Gallo) የመሳሰሉት የታሪክ ጸሐፊዎች በየድርሰታቸው ገልጸዋል።

« እንዲት ከሥልጣኔ ርቃ በጭለማው ዓለም ውስጥ የምትኖር፤ ዘመናዊ የጦር መሣሪያ የሌላት፤ ኢትዮጵያ የምትባል የጥቁሮችና የድሆች አገር፤ የነ ጁሴፔ ማዚኒን፤ የነ ካቡርንና የነጋሪባልዲን ጣልያን ተዋግታ ድል አደረገች » ተብሎ በየጋዜጣው የተጻፈውን፤ የአሥራ ሦስት ዓመቱ ልጅ ቤኒቶ ሙሶሊኒ ሲያነብ፤ ከጓደኞቹ ይበልጥ እጅግ መቆጨቱንና ማዘኑን የሚማርበት ተማሪ ቤት መምህራኖች ምስክርነታቸውን ሰጥተዋል ይባላል። ከዚህም በላይ ቤኒቶ «... የክሪስፒ መንግሥት በጣልያን ታሪክ ላይ የመዘገበውን የውርደት ምዕራፍ፤ የኛ ትውልድ ብድሩን መመለስና የአገራችንን ስም በሌላ በአዲስ ታሪክ ማደስ ያስፈልጋል ... » ብሎ ለመሰል ጓደኞቹ ምኞቱን ገልጿል እየተባለ ይነገርለታል።

መቼም፤ በታሪክ ብዙ ጊዜ እንደምንሰማውም ሆነ እንደምናየው፤ አንድ ሰው ከአንቱል ቦታ ተነስቶ ባልተጠበቀ መንገድ ከከፍተኛ የአገር መሪነት ደረጃ ላይ ሲደረስ፤ በልጅነቱ እንዲህ ብሎ ነበር .... በወጣትነቱ እንዲሁ ያስብ ነበር ... እየተባለ የማድነቂያ አጀብ እየተደረገ ይወራለታል። እንደዚሁም ቤኒቶ ገና በአሥራ ሦስት ዓመቱ ጣልያን አድዋ ላይ የደረሰበትን ውርደት የኛ ትውልድ መመለስ አለበት ብሎ ተናግሮ ነበር የተባለው፤ ከዐርባ ዓመታት በኋላ እሱ ራሱ ዱቼ ሙሶሊኒ የአገሩ መሪ ሆኖ ኢትዮጵያን በወረረ ጊዜ ነው። ቤኒቶ ገና በልጅነቱ ይህን

ሐሳብ መወርወሩና ከዚያም ይህ ምኞቱ አብሮት አድጐ ለፍጻሜ ያደረሰው መሆኑን ከአፍ ታሪክ በስተቀር የሰነድ መረጃ አይገኝለትም።

ቤኒቶ፣ ከሕፃንነቱ ጀምሮ የጉልማሳ ዕድሜ ላይ እስከደረሰበት ጊዜ ከነበረው፣ ከዚያ ሁሉ አጉል ጠባይና ምግባር ተሻሽሎ፣ ከዚያ ሁሉ የሕይወት ፈተናዎች አልፎ፣ መጀመሪያ የሶሲያሊስቶቹ የአቫንቲ ጋዜጣ ዋና አዘጋጅ ሆኖ እንደዚያ ሲጨፍር፣ ቀጥሎ ደግሞ የሊበራሎቹ ጋዜጣ መሪ ሆኖ እንደዚያ ሲዘል፣ በዚያ በታወቀው ብዕሩ አንድም ጊዜ ጣልያን የአድዋን ብድር መመለስ አለባት የሚል አስተያየት አልሰነዘረም። ስለዚህ፣ የታሪኩን ሂደት እየተከተልን ከሄድን፣ ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን ለመውረር ያሰበውና የወሰነው፣ የአገሩ የጣልያን ፈላጭ ቆራጭ መሪ ሆኖ ከኖረ ከአሥር ዓመታት በኋላ እንጂ፣ ከዚያ በፊት ዝግጅት ጀምሮ ነበር ለማለት የሚያስችል መረጃ አላገኘንም።

እ.ኤ.አ 1923 ዓ.ም፣ ሙሶሊኒ በጠቅላይ ሚኒስትርነት ጣልያንን መምራት ከጀመረ ከአሥራ አንድ ወራት በኋላ፣ ኢትዮጵያ በዤኔቭ የመንግሥታት ማህበር አባል እንድትሆን የቀረበውን ጥያቄ እንግሊዞች ለዚህ ደረጃ ብቁ አይደለችም ብለው ሲቃወሙ፣ የጣልያን መንግሥት ከፈረንሣይ ጋር ሆኖ ከፍ ያለ ድጋፉን ሰጠ። በዤኔቭ የፈረንሣይ መልዕክተኛ ሙሴ ደ-ዡቨኔል (De Jouvenel) ባደረገው የድጋፍ ንግግር፣ « ... የአገሮችን ነፃነትና መብት በመጠበቅ፣ ኢትዮጵያ የዓለም ቤተሰብ አባል ሆና እንድትመዘገብ ማድረግ ትክክለኛ ውሳኔ ነው ... » ሲል የሙሶሊኒ መልዕክተኛ ኮንት ቦኒን ሎንጋሬ (Count Bonin Longare) ደግሞ በበኩሉ « ... **ኢትዮጵያ ከዓለም አቀፍ ጉዳዮች ብትርቅም፣ የራሷ የሆነውን ባህሏንና ነፃነቷን ጠብቃ፣ በሃይማኖቷ ፀንታ፣ ለረዥም ዘመናት ብቻዋን የኖረች ስለሆነ፣ ዛሬ የመንግሥታት ማህበር አባል አድርጐ ሲቀበላት፣ ትክክለኛ የሆነ ፍትሕ እንደ ሰጣት የሚቆጠር ይሆናል** ... » በማለት እጅግ ከፍ ያለውን ድጋፍ ሰጠ። ይህ ከዚህ በላይ የተገለጸው ከፈረንሣይና በተለይም ከሙሶሊኒ መንግሥት ለኢትዮጵያ የቀረበው ትልቅ ድጋፍ፣ የእንግሊዞችን ተቃዋሚነት የደመሰሰው ስለሆነ፣ እ.ኤ.አ በመስከረም 28 ቀን 1923 ዓ.ም ኢትዮጵያ በዤኔቭ የሚገኘው የዓለም መንግሥታት ማህበር አባልነቷ ጸድቆ የማህበርተኛነት የክብር ወንበሯን ለመረከብ ችላለች። በዚህ ጉዳይ የንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱና የአልጋወራሽ ተፈሪ ዋና መልክተኛ ሆነው በዤኔቭ ጉባኤ ላይ የተካፈሉት ራስ ናደው አባወሎ፣ ኢትዮጵያ የዤኔቩ ማህበር አባል መንግሥት መሆኗ በኦፊሲየል እንደተገለጸ፣ ወደ አዲስ አበባ የላኩት ቴሌግራም ሊጠቀስ የሚገባው ነው። « .... **አገራችን ኢትዮጵያ የመንግሥታት ማህበር አባል እንድትሆን ከተሟገቱልንና ከረዱን አገሮች መካከል፣ ጣልያን ቅድሚያውን ይዛ መገኘቷ የእግዚአብሔር ተአምር ነው ከማለት በስተቀር ሌላ ምክንያት የለንም። ጠላታችን ሆና የኖረ አገር፣ ይህን ያህል ይረዳናል ብለን እንኳንስ በውናችን በሕልማችንም የሚታየን አልነበረም። የእንግሊዝን ተቃዋሚነት ያሸነፈልንና የጣልያንን ደጋፊነት የባረከልን ፈጣሪያችን ስለሆነ፣ ምስጋና ይግባው ከማለት ሌላ የምንጨምረው የለም** ... »

ራስ ናደው እንደ ገለጹት ሁሉ፣ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥት ባለሙሉ ሥልጣን የሆኑት አልጋ ወራሽ ተፈሪ፣ ለዤኔቩ ማህበር አባልነት ኢትዮጵያ ድጋፍ ታገኛለች ብለው በእርግጠኛነት የጠበቁት፣ ከፈረንሣይና ከእንግሊዝ መንግሥታት እንጂ፣ ከጣልያን አልነበረም። በዚያን ጊዜ የሙሶሊኒም ጣልያን በዓለም ጉዳይ ላይ ይህን ያህል ተደማጭነት ስለሌላት፣ የእሷ ተቃውሞ ቢመጣም ሊጉዳን ይችላል ተብሎ አልታሰበም ነበር። እንግሊዞች ግን የኢትዮጵያ

ጉዳይ በመንግሥታት ማህበር በዋናው ኮሚቴ በሚጠናበት ጊዜ፣ አገሪቱ እጅግ ኋላ ቀር ከመሆኗም በላይ፣ የሰውን ልጅ "ባሪያ " እያለች ንግድ የምታካሂድ ስለሆነች፣ ለመንግሥታት ማህበር አባልነት አልደረሰችም በማለት፣ ዘርዝረው ያቀረቡትን ተቃውሞ፣ ጣልያንና ፈረንሣይ መክተው በመታገላቸው፣ የጠቅላላው ጉባኤ የኢትዮጵያን ማህበርተኛነት ተቀብሎ ለማጽደቅ ቻለ።

የዚህን ታሪክ ሂደት ስንመለከት፣ እ.ኤ.አ በ1923 ዓ.ም ሙሶሊኒ የንግሥተ ሳባን አገር ወርሬ ቅኝ ግዛቴ አደርጋታለሁ ብሎ በእርግጥ የሚዘጋጅ ቢሆን ኖሮ፣ እንግሊዞችን እንደዚያ ተቃውሞ፣ ኢትዮጵያ በዓለም መንግሥታት ማህበር ነፃነቷ የተረጋገጠላት አገር እንድትሆን ያንን ያህል ድጋፍ ለምን ሰጠ ? የሚል ጥያቄ ሊቀርብ ይችላል።

በርግም የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አምባሳደር በነበርኩበት ጊዜ፣ በዚህ በመንግሥታት ማህበር አባልነት ጉዳይ፣ ፋሽስቱ ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን የደገፈበት ምክንያት ምን እንደሆነ ለማወቅ፣ ከጣልያን የፖለቲካ መሪዎች አሜንቶሬ ፋንፋኒን፣ አልዶ ሞሮንና ሳንድሮ ፔርቲኒን፣ ከታወቁት የታሪክ መምህራኖች መካከል ደግሞ፣ ፕሮፌሰር ዴ-ፌሊቼን በተለያዩ አጋጣሚዎች አነጋግሬያቸው ነበር።

<u>ሳንድሮ ፔርቲኒ</u> ፣ የሶሲያሊስት ፓርቲ አባልና የታወቀ ፀረ ፋሽስት በመሆኑ፣ በሙሶሊኒ መንግሥት ዘመን ብዙ ጊዜ በእስር የተጉላላና ኋላም በስደት የችግሩን ዘመን ያሳለፈ ነው። ከፋሽስት መውደቅ በኋላ ነፃነት ሲመለስ፣ ለብዙ ጊዜ የፓርላማው የሕዝብ ምክር ቤት ፕሬዚዳንት ሆኖ ከሠራ በኋላ፣ በመጨረሻው ለሰባት ዓመታት የጣልያን ሬፑብሊክ ፕሬዚዳንት ሆኖ ነበር። ሳንድሮ ፔርቲኒ በፋሽስት ዘመን በእስር ቤት በሚኖርበት ጊዜ፣ ከኢትዮጵያ ታስረው ከመጡት ከአንዳንድ መኳንንቶች ጋር ተዋውቆ አንዳንድ ትዝታዎች አሳድሯል። « ... ለምሳሌ ራስ እምሩ ኃይለ ሥላሴ በእስር ቤት ሆነው፣ የነበራቸውን የመንፈስ ጠንካራነት፣ ክብራቸውን ለመጠበቅ የሚያደርጉትን ጥንቃቄ፣ በተለይም በፋሽስቶቹ የጦርና የሲቪል ባለሥልጣኖች ላይ የሚያሳዩትን ንቀት፣ ምንጊዜም ልረሳው አልችልም። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ እ.ኤ.አ በ1970 ዓ.ም ጣልያንን ለመጎብኘት ሲመጡ፣ የፓርላማው ፕሬዚዳንት በመሆኔ አውሮፕላን ማረፊያ መገኘት ቢኖርብኝም፣ በተለይ ለማየት የጓጓሁት የእስር ቤት ወዳጄን ራስ እምሩን ነበር። ከንጉሠ ነገሥቱ በኋላ ራስ እምሩን እጃቸውን ጨበጬ የጋለ ሰላምታዬን ሳቀርብላቸው፣ ሊያስታውሱኝ አልቻሉም። ... እኔ ሳንድሮ ፔርቲኒ ነኝ ... ብላቸውም ትዝ ልላቸው አልቻለም። ሆኖም ከሠላሳ አምስት ዓመት በኋላ ለመጀመሪያ ጊዜ ሳያቸው በጣም ደስ አለኝ ... »

እ.ኤ.አ በ1923 ዓ.ም ኢትዮጵያ የመንግሥታት ማህበር አባል ስትሆን፣ የሙሶሊኒ መንግሥት ስለአደረገው ድጋፍ ፔርቲኒ የሰጠኝ አስተያየት ከሌሎቹ ሁሉ የተለየ ነበር። « ... እናንተ ኢትዮጵያውያኖች የዛሬዎቹም ሆናችሁ የነገዎቹ ትውልዶች፣ ሙሶሊኒ አገራችሁ ሊግ ኦፍ ኔሽን እንድትገባ መደገፋን በቁም ነገር መመልከት የለባችሁም። ሙሶሊኒ ቀዥቃዣና ዕብድ ስለሆነ፣ ዛሬ የሚሠራውንና ነገ የሚያስበውን አዛምዶ የመመዘን ችሎታ አልነበረውም። በሊግ ኦፍ ኔሽን አዳራሽ ኢትዮጵያን ሲደግፍ፣ በቅርቡ ምን ጥቅም እንደሚያመጣለት፣ በሩቅ ዘመን

ደግሞ ምን ችግር እንደሚፈጥርበት አጥንቶ አልተረዳም። ፈረንሣዮች እኛ ኢትዮጵያን እንደግፋለን ሲሉት፤ እኔስ ከእናንተ በምን አንሳለሁ? ብሎ ደጋፊ ሆኖ አጨበጨበ እንጂ፤ ኢትዮጵያን በማስደሰት ወዳጄ አደርጋታለሁ ወይም ደግሞ ኢትዮጵያ ውለታዬን አስባ ወዳጅ ታደርገኛለች ብሎ አይደለም። በመሠረቱ፤ በዚህ ዓለም የነገሡት ዕብድ የሆኑት መሪዎች ሁሉ፤ የአጭርና የረዥም ጊዜ የተጠና ፕላን የላቸውም። ዛሬ ሲደግፉት የነበረውን ነገ እንደሚዘልቁበት ማረጋገጫ የለም። እንደዚሁም ሙሶሊኒ፤ ኢትዮጵያ የመንግሥታት ማህበር አባል እንድትሆን ከረዳት ከአሥር ዓመታት በኋላ፤ ነፃነቷን ለመግፈፍና ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ ጦር ሲልክባት፤ ከአሥር ዓመት በፊት ለዚች አገር ያደረገው ምን እንደነበረ አላስታወሰም። ስለዚህ፤ እናንተ ኢትዮጵያውያኖች ሙሶሊኒ ምን አድርጐልን ነበር? እያላችሁ በመመራመር ጊዜያችሁን አታጥፉ። ለእናንተ ያደረገላችሁ ምንም ቁም ነገር የለም። ሙሶሊኒ በእናንተ ላይ የፈጸመው ግፍና በደል ብቻ ስለሆነ፤ በዚሁ ላይ ብቻ ታሪካችሁን በሚገባ ለመገንባትና ከትውልድ ወደ ትውልድ የሚተላለፍ እንዲሆን ከማድረግ በስተቀር፤ ሌላ ነገር መጨመር የለባችሁም ... » ከዚህ በላይ እንደታየው፤ ለፕሬዚዳንት ፔርቲኒ ያቀረብኩት ጥያቄና የተሰጠኝ መልስ የተለያየ መሆኑ ለማንም ግልጽ ነው። የሳንድሮ ፔርቲኒ ፀረ ፋሽስትነትና በሙሶሊኒም ላይ ያለው ጥላቻ እጅግ የጠነከረ ከመሆኑም በላይ፤ ሰውየው በተፈጥሮው ብስጩና ችኩል ስለሆነ፤ ለጥያቄዬ የጠበቅኩትን ቀጥታ መልስ አላገኘሁም። እኔ የጠየቅሁት ሙሶሊኒ በዚያን ጊዜ ኢትዮጵያን ለመርዳት ምን ምክንያት ኖሮታል? የሚል እንጂ፤ የሱ ውለታ አለብን ወይ ብዬ ለመመራመር አልነበረም።

<u>አሜንቶሬ ፋንፋኒ</u> ፤ ብዙ ጊዜ ጠቅላይ ሚኒስትርና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የነበረ፤ ከሁለት ጊዜ በላይ የሴናው ፕሬዚዳንት የሆነ፤ በወጣትነቱም ዘመን በሚላኖ ዩኒቨርሲቲ የፋሽዝም ፍልስፍና አስተማሪ ሆኖ ያገለገለ ነው።

ሙሶሊኒ፤ ኢትዮጵያ የመንግሥታት ማህበር አባል እንድትሆን ድጋፍ የሰጠበት ምክንያት ምን ኖርዋል ? ለሚለው ጥያቄ አሜንቶሬ ፋንፋኒ የሰጠው መልስ አጭር ነው። « ... በዚያን ዘመን ዱቼ ኢትዮጵያን የመውረር ዕቅድ ያለው ቢሆን ኖሮ፤ ከእንግሊዞች አስተያየት ተለይቶ ያንን የሚያህል የሞቀ ድጋፍ አይሰጥም ነበር። ቀጥታ መቃወሙ ደግሞ የጠላትነት መንፈስ የሚያሳይብኝ ይሆናል ብሎ ከሠጋ፤ አንዳንድ አገሮች እንዳደረጉት፤ በዤኔቭ ስብሰባ ላይ ጉዳዩ ሲነሣ፤ በንግግሩም ሆነ በክርክሩ ላይ የጣልያን መልዕክተኛ ተካፋይ ሳይሆን በዝምታ ማለፍ ይችል ነበር ... »

<u>አልዶ ሞሮ</u> ፤ አምስት ጊዜ በጠቅላይ ሚኒስትርነት ጣልያንን የመራ፤ አሥራ ስድስት ጊዜ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር በመሆን በዓለም ላይ እጅግ የታወቀ ዲፕሎማት፤ የኢትዮጵያም ወዳጅ የነበረ ሰው ነው። በሊግ ኦፍ ኔሽን ጉዳይ ስለ ሙሶሊኒ እርዳታ የሰጠኝ አስተያየት የሚከተለው ነው።

« ... እ.ኤ.አ በመስከረም 1923 ዓ.ም ሙሶሊኒ ጣልያንን በዲክታተርነት መምራት ከጀመረ ዓመት አልሞላውም። በዚያን ሰዓት የሙሶሊኒ ዋና ጥረት፤ በአገሩ ውስጥና በውጭው ዓለም፤ የጣልያን መሪ መሆኑን ለማሳወቀና ለማሳመን ስለሆነ፤ ኢትዮጵያን ቅኝ ግዛት አደርጋታለሁ የሚል ዕቅድ አልነበረውም። ጉዳዩን ደህና አድርጐ መመልከት የሚያስፈልገው፤ በዚያን ጊዜ ኢትዮጵያ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል እንድትሆን፤ ከታላላቅ አገሮች መካከል የመጀመሪያውን ድጋፍ የሰጡት

## ደራሲው ከጣልያን መሪዎች ጋር



ሳንድሮ ፔርቲኒ የሬፑብሊኩ ፕሬዚዳንት



አሜንቶሬ ፋንፋኒ የሴኔት ፕሬዚዳንት



አልዶ ሞሮ ጠቅላይ ሚኒስትርና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር

ፈረንሣዮች መሆናቸውን ነው። የፈረንሣዮች ድጋፍ የተመሠረተው ደግሞ፣ በመንግሥታት ማህበር ውስጥ፣ ኢትዮጵያ በሚያስፈልገን ቦታ ሁሉ በድምጿ ደጋፊያችን ትሆናለች በሚል የጥቅም ሐሳብ መሆኑ የተሰወረ አይደለም። የሙሶሊኒም መንግሥት የኢትዮጵያን የአባልነት ጉዳይ እንዲደግፍ የጠየቁት ፈረንሣዮች ናቸው። በዚያን ዘመን፣ ፋሽስት ሥልጣን ከያዘበት ጊዜ ጀምሮ በፈረንሣይና በጣልያን መንግሥታት መካከል ያለው ግንኙነት በጣም የቀዘቀዘ ስለነበረ፣ ሙሶሊኒ ከፈረንሣይ በኩል የቀረበለትን ጥያቄ ተቀብሎ ለኢትዮጵያ ድጋፉን የሰጠው፣ በዚህ ምክንያት ሮምና ፓሪስ በወዳጅነት ሊቀራረቡ ይችላሉ በሚል ተስፋ ነው ሊባል ይቻላል። እርግጥ የሚያስገርመው፣ ከሙሶሊኒ ለኢትዮጵያ የተሰጠው የድጋፍ ዲስኩር፣ በጉዳዩ ባለቤቶች ነን ከሚሉት ከፈረንሣዮቹ በልጦ መገኘቱ ነው። የሆነ ሆኖ የሁለቱ መንግሥታት ማለት የፈረንሣይና የጣልያን መተባበር፣ ኢትዮጵያን የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል እንድትሆን ለማስደረግ መቻሉ የሚካድ አይደለም። ሙሶሊኒ ግን በእኔ ግምት ይህን ድጋፍ የሰጠው፣ ለፈረንሣዮች ወዳጅነት ሲል ነው እንጂ፣ ለኢትዮጵያ አስቦ አለመሆኑ የሚያከራክር አይደለም ... ››

<u>ፕሮፌሰር ሬንሶ ደ-ፌሊቼ ፣</u> በፋሽዝም ፍልስፍና ብዙ ጥናት ያደረገ፣ ኊላም በሮማ ዩኒቨርሲቲ በመምህርነቱና በታሪክ ድርሰቱ ብዙ የታወቀ ሰው ነው። ለሌሎቹ የፖለቲካ መሪዎች እንዳቀረብኩት ሁሉ፣ ለጠየቅኩት ጥያቄ የሰጠኝ መልስ የሚከተለውን ነው።

‹‹ ... እንደሚታወቀው፣ ሙሶሊኒ በትምህርት በስሎ ያደገ፣ ወይም ራሱ ተመራምሮ ዕውቀቱን ያስፋፋ ሰው አይደለም። በጠባዩም ከሌሎቹ በዓለም ላይ ሲያስቸግሩ ከኖሩት ዲክታተሮች የተለየ የሚያደርገው፣ በሚሰጠው ቃል የማይፀና፣ በሚወስደው እርምጃ በጥልቀት የማያስብ ችኩል ሰው መሆኑ ነው። በሊግ ኦፍ ኔሽን ኢትዮጵያ አባል እንድትሆን እሱ ራሱ ያሰበበት ጉዳይ አልነበረም። የኢትዮጵያ መንግሥትም እርዳኝ ብሎ ልመና አላቀረበለትም። በዚያን ዘመን የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትር የነበረው ሬሞንድ ፖንካሬ፣ ኢትዮጵያን የመንግሥታት ማህበር በአባልነት እንዲቀበላት፣ የጣልያን ድጋፍ ከእኛ ጋር ቢተባበር አመሰግናለሁ ብሎ መልዕክት ሲልክበት፣ ይህ ጉዳይ ምክንያት ሆኖ ከፈረንሣይ መንግሥት ጋር መልካም ግንኙነት ለመዘርጋት ይረዳኛል በሚል ተስፋ፣ ችኩሉ ሙሶሊኒ ወዲያውኑ ሮጦ የእንግሊዞች ተቃዋሚና የኢትዮጵያ ደጋፊ ሆኖ ፈረንሣይን አስደሰተ። ይሁን እንጂ፣ ኢትዮጵያ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል ከሆነች በኊላ፣ ሙሶሊኒ እንደተመኘው የፈረንሣይና የጣልያን መንግሥታት ግንኙነት በፍቅርና በወዳጅነት አልቀጠለም። በፋሽስት የዲክታተር አመራር ምክንያት ፈረንሣዮች የጣልያኑን መሪ እየነቀፉ ግንኙነታቸውን በማቀዝቀዝ ለአሥር ዓመታት ቀጥለው ነበር። ፈረንሣይና ጣልያን የተቀራረቡት የሙሶሊኒ ኃይልና ተደማጭነት ከገነነ በኊላ እ.ኤ.አ ከ1933 ዓ.ም ጀምሮ ነው... ›› ሲል፣ የታወቀው መምህር ፕሮፌሰር ደ ፌሊቼ አስተያየቱን ሰጥቷል።

<u>እ.ኤ.አ በሰኔ ወር 1924 ዓ.ም፣</u> ሙሶሊኒ የአገሩ መሪ ከሆነ ከአንድ ዓመት ከአሥር ወር በኊላ፣ የኢትዮጵያ ባለሙሉ ሥልጣን አልጋወራሽ ራስ ተፈሪ መኰንን ጣልያንን በኦፊሲየል ለመጐብኘት ሮም ሲደርሱ፣ ዱቼ ከንጉሡ ጋር ባቡር ጣቢያ በመገኘት የክብር አቀባበል አድርጉላቸዋል። ከዚህም በኊላ፣ አልጋወራሽ ጉብኝታቸውን በጀመሩ በሁለተኛው ቀን፣ ሙሶሊኒ ፓላሶ ቬኔሲያ (Palazzo Venezia)

እንግዲህ ! ንጉሠ ነገሥቱ ለፈረንሣዊው ጋዜጠኛ የገለጹትን አስተያየት ስንመለከት፤ በዚያን ጊዜ ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን ለመውረር አለማሰቡን ለማመን የሚያስችል ይሆናል።

<u>እ.ኤ.አ በ1925 ዓ.ም፤</u> የእንግሊዝና የጣልያን መንግሥታት ለጋራ ጥቅማቸው በኢትዮጵያ ጀርባ አንድ ስምምነት ያደርጋሉ። ይኸውም፤ እንግሊዝ የጣናን ባሕር በመገደብ ለቅኝ ግዛቶቹ ለሱዳንና ለምስር አገሮች ጥቅም እንዲውል ለማድረግ ሲሆን፤ ጣልያን ደግሞ ቅኝ ግዛቶቹን ሱማሌንና ኤርትራን በኢትዮጵያ መሬት ላይ አቋርጦ የሚያገናኝ የባቡር ጉዳና ለመዘርጋት ነበር። እነዚህ ሁለቱ መንግሥታት እርስ በርሳቸው ተነጋግረው ስምምነታቸውን ካጠናቀቁ በኋላ፤ አዲስ አበባ ባሏቸው የዲፕሎማቲክ ሚሲዮኖች በኩል አልጋወራሽ ተፈሪ እንዲያውቁት ሲያደርጉ፤ በኢትዮጵያ መንግሥት ዘንድ ጉዳዩ እጅግ አሳሳቢ ሆኖ ታየ። ወዲያውም ራስ ተፈሪ በዠኔቭ ለሚገኘው የመንግሥታት ማህበር ባስተላለፉት ቴሌግራም፤ « ... የታላቋ ብሪታንያ እና የጣልያን መንግሥታት ኢትዮጵያን በምንም ረገድ ሳያማክሩ፤ የጣናን ባሕር ለመገደብና፤ በኢትዮጵያ ግዛት ላይ አቋርጦ ሱማሌንና ኤርትራን የሚያገናኝ የባቡር መንገድ ለመዘርጋት ያደረጉት ስምምነት፤ ያገሬን ነፃነትና መብት የሚዳፈር መሆኑ እንዲታወቅልኝ ... " ሲሉ፤ አመለከቱ። የመንግሥታቱ ማህበር ከኢትዮጵያ የደረሰውን ማመልከቻ ለኮሚሲዮኑ አቅርቦ እንዲታይ ከማድረጉ በፊት፤ የእንግሊዝና የጣልያን መንግሥታት ስሕተታቸውን ስለአወቁ፤ ለራስ ተፈሪ ከእውነት የራቀ የተጭበረበረ ምክንያት በመስጠት ይቅርታ ከጠየቁ በኋላ፤ ጉዳዩ በሰላም ተዘጋ።

ይሁን እንጂ፤ በዚህ ጉዳይ የኢትዮጵያ መንግሥት ከእንግሊዝ ይልቅ በጣልያን ላይ ከፍተኛ ቅሬታ አደረበት። በሰኔ 1924 ዓ.ም ራስ ተፈሪ ጣልያንን በጐበኙ ጊዜ በሁለቱ አገሮች መካከል ከፍተኛ የወዳጅነትና የመቀራረብ መንገድ ተዘረጋ ተብሎ ብዙ የደስታ መግለጫዎች ከተደረጉ በኋላ፤ ልክ በዓመቱ የሙሶሊኒ መንግሥት ከእንግሊዝ ጋር ተንኮል ሲሠራ በመገኘቱ፤ ከእንግዲህ ወዲህ በጣልያን ላይ ጥርጣሬ ማድረግና መከታተል ያስፈልጋል ተብሎ በከፍተኛ ደረጃ ስብሰባ ተወሰነ።

<u>እ.ኤ.አ 1928 ዓ.ም ፤</u> የፋሽስቱ የሙሶሊኒ መንግሥት፤ ሐሳቡን ራሱ አመንጭቶ በሌላ መንገድ ከንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ጋር የተለየ ወዳጅነት ለመመሥረት ቀረበ። እ.ኤ.አ ነሐሴ 2 ቀን 1928 ዓ.ም በኢትዮጵያና በጣልያን መንግሥታት መካከል ለሐያ ዓመታት ጸንቶ የሚኖር ወዳጅነትን ለማስፋፋትና የጋራ ችግሮችን በሰላማዊ መንገድ ለመፍታት የሚያስችል ስምምነት ተደረገ። በዚሁም ስምምነት ውስጥ ኢትዮጵያ በአሰብ በኩል የባሕር መተላለፊያ በር እንዲኖራት የጣልያን መንግሥት መፍቀዱንና፤ ከአሰብም እስከ ደሴ ድረስ ሁለቱ መንግሥታት ተባብረው መንገዱን እንደሚሠሩ ቃል መግባታቸው ተገለጸ።

የኢትዮጵያ መንግሥት ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴ የሆኑት ራስ ተፈሪ መኰንን፤ በዚህ በተፈረመው ውል አንድ ዓይነት ተስፋ አደረባቸው። ይኸውም፤ በውሉ ውስጥ በሰባት አንቀጾች ከተዘረዘሩት ጉዳዮች መካከል፤ ሦስቱን አልጋ ወራሹ አጥብቀው የሚፈልጓቸው በመሆናቸው ነው። እነዚህም፦

**አንቀጽ ሁለት፤** የኢትዮጵያና የጣልያን መንግሥታት አንዳቸው የአንዳቸውን ነፃነት የሚነካ ወይም የሚጐዳ ነገር እንዳያደርጉ በየበኩላቸው ግዴታ ገብተዋል።

**አንቀጽ አምስት፤** ሁለቱ መንግሥታት በመካከላቸው የሚነሣውን አለመግባባት በዲፕሎማቲክ መንገድ መጨረስ ካቃታቸው፤ በጦር ኃይል ሳይሆን፤ ከሁለቱም ወገኖች ለሽምግልና በሚመረጡ ዳኞች እንዲታይላቸው ለማድረግ ግዴታ ገብተዋል።

**አንቀጽ ስድስት፤** ይህ ሁለቱ መንግሥታት ተስማምተው በየፊርማቸው ያጸደቁት ውል፤ ወደ ዤኔቭ የመንግሥታት ማህበር ተልኮ በኦፊሲየል ዶክመንት ሆኖ እንዲመዘገብ ይደረጋል። የሚሉት ናቸው።

እንግዲህ ! በራስ ተፈሪ መኰንን በኩል ይህ ከሙሶሊኒ መንግሥት ጋር የተፈረመው ውል፤ ለሐያ ዓመታት የሚጸና ነው ስለተባለ፤ ኢትዮጵያ በዘመናዊው ሥልጣኔ እየተራመደች፤ የነፃነቷንም መከላከያ ኃይል ለማጠንከር ሰፊ የሆነ የሰላም ዘመን ይኖራታል፤ የሚል ከፍ ያለ ተስፋ ተደርጐ ነበር። ሙሶሊኒ በበኩሉ የፈረመውን ይህን ስምምነት ለምን ያህል ጊዜ አክብሮ እንደጠበቀው፤ የታሪኩን ሂደት በመከተል ወደፊት እናገኘዋለን።

Reference: societé des nations Journal Nº 1615